# የመጨረሻው

# እስትንፋስ

## በዑስማን ኑሪ ቶኘባሽ


ትርጉም፡- አህመድ ሁሴን (አቡ ቢላል)

አርትኦት፡- ሐሰን ታጁ



***አሳታሚ፡- አልበያን ሊሚትድ***

***ስልክ ቁጥር ፡- 0913878788 ወይም 0911051025***

***<u>አዲስ አበባ ኢትዮጵያ</u>***

# መግቢያ

ሞት አይቀሬ ነገር፣ የሁላችንም እጣ ፈንታ። ይህን ሁላችንም እናውቃለን፣ ሁላችንም እንረሳለን። አሟሟቱን ያማረ እንዲሆን የማይሻ ማን አለ! ሕይወት የቱን ያህል ብትረዝምም አጭር ናት። የቱን ያህል ብታምርም አስቀያሚ ናት። ሞት ሲመጣ እድሜ ሙሉ የለፋንለት ንብረት ይከዳናል። ዘመድ ወዳጅ ይተወናል። ከስራችን ጋር እንፋጠጣለን። የመቃብርን አለም እንጋፈጣለን።

የመጨረሻ እስትንፋሱ ያማረለት ታደለ። ይህችን አለም በሸሃዳ የተነጠለ ተሳካለት። በእስልምና የተለያት አማረለት። ነብያት ‹‹ሙስሊም አድርገህ ግደለን›› በማለት አላህን ሲማጸኑ ቁርአን ውስጥ በበዛት ማንበባችን ትኩረትን የሚስብ ነገር ነው። ሙስሊም ሆኖ መሞት፣ የመጨረሻ እስትንፋስ ሸሃዳ መሆኑ ከባድ ነገር መሆኑን ያመለክታል።

አሟሟታችን ያምር ዘንድ አኗኗራችን መስተካከል እንዳለበት ዑለሞች ይመክሩናል። ሕይወቱን አላህን በመታዘዝና በኢባዳ ያሳለፈ በመጨረሻ የዘራውን ያጭዳል። ሸሃዳን ይወፈቃል። ኢማኑን በልቦናው እንደቋጠረ ይህችን አለም ይሰናበታል። በአንጻሩ ሕይወቱ ከአላህ ትእዛዝ ውጭ ሆኖ ያሳለፈ አሟሟቱም ይከፋል። ሸሃዳ ማለት ተራራ የመግፋት ያህል ይከብደዋል።

ቱርካዊው አሊም ሸህ ዑስማን ኑሪ ቶፕባሽ የመጨረሻ እስትንፋሳችን ያማረ፣ ፍጻሜያችን የሰመረ ይሆን ዘንድ በዚህች መጽሐፍ እጅግ ጠቃሚ ትምህርት አቅርበውልናል። መጽሐፏ ሁላችንንም የሚመለከት ሐሳብ ይዛለችና በጥሞና እናንብባት። አንብበንም በልቦናችን ውስጥ እናሳድራት። ወደተግባርም እንለውጣት።

አላህ ለሁላችንም መልካም ፍጻሜ (ሁስነል ኺታም) ይለግሰን። አሜን!

ሐሰን ታጁ

ሕዳር 2003

# ምዕራፍ አንድ

# ለመጨረሻው እስትንፋስህ ተዘጋጅ

ኃያሉ አላህ ዘለዓለም የመኖርን ባሕሪ ለራሱ ብቻ በማድረግ ሌላውን ፍጡር ሁሉ እንዲጠፉ ጥንቱኑ ወስኗል። አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ كُلُّ مَنْ عَلَيْهَا فَانٍ ﴿٢٦﴾ ﴾ الرحمن: ٢٦

‹‹ በእርሷ (በምድር) ያለው ሁሉ ጠፊ ነው። ›› (አር-ራህማን፡ 26)

ፍጡራን ሁሉ የሚጠፉበት ሰበብ ወይም መገለጫ ደግሞ ያው አይቀሬ የሆነው ሞት ነው።

﴿ كُلُّ نَفْسٍ ذَآئِقَةُ ٱلْمَوْتِ ﴾ الأنبياء: ٣٥

‹‹ ነፍስ ሁሉ ሞትን ቀማሽ ናት›› (አል-አንቢያ፡ 35)

በዚህም ምክንያት የሰው ልጆች በዚህች ምድር ላይ ኮንትራታቸውን አጠናቅቀው ከመሄዳቸው በፊት ስለዚህ መራራ የሆነ እጣ ፈንታቸው ደግመውና ደጋግመው ማሰብ ይኖርባቸዋል። አላህ በተጨማሪም እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَجَآءَتْ سَكْرَةُ ٱلْمَوْتِ بِٱلْحَقِّ ذَٰلِكَ مَا كُنتَ مِنْهُ تَحِيدُ ﴿١٩﴾ ﴾ ق: ١٩

‹‹የሞትም መከራ እውነቱን ነገር ታመጣለች። (ሰው ሆይ!) ይህ ያ ከርሱ ትሸሸው የነበረው ነው። (ይባላል)›› (ቃፍ 19)

የሰው ልጆች በዚህች ዓለም ላይ ተፈጥረው እንዲገኙ የመደረጋቸው ምስጢር ለፈተና እንደመሆኑ በሕይወት ዘመናቸው ዋነኛውና ታላቁ ግባቸው ሊሆን የሚገባው በጀነት ቦታ ማግኘት ነው። ይህንንም

ለማድረግ የአለማቱ ሁሉ ጌታ የሆነውን አላህን የሚያስደስቱ መልካም ሥራዎችን በብዛትና በጥራት መሥራት ይጠበቅባቸዋል፡፡ ይህን ማድረግ ያለባቸው ለምንድን ነው? ሰላማዊና አላህ የሚወደውን ንጹህ ቀልብ (ልብ) ይዘው ለመቅረብ ነው፤ ይህም ንጹህ ልብ (ቀልበን ሳሊም) በሚከተለው የቁርዓን አንቀጽ ተገልጿል፡-

﴿يَوْمَ لَا يَنفَعُ مَالٌ وَلَا بَنُونَ ﴿٨٨﴾ إِلَّا مَنْ أَتَى ٱللَّهَ بِقَلْبٍ سَلِيمٍ ﴿٨٩﴾﴾ الشعراء: ٨٨ - ٨٩

‹‹ገንዘብም ልጆችም በማይጠቅሙበት ቀን፣ ወደ አላህ በንጹህ ልብ የመጣ ሰው ቢሆን እንጂ፡፡ ›› (አሽ-ሹአራ፡ 88-89)

ይህን ማድረግ የሚቻልበት ብቸኛው መንገድ ነፍስን ሥርዓት በማስያዝ ሲሆን ይህ እውነተኛ ሥርአት ደግሞ የአላህና የመልእክተኛውን (ሰ.ዐ.ወ.) ትዕዛዛት በሚገባ በመጠበቅ ነው፡፡ የአላህን ትዕዛዛት በቀጥታ የእርሱ ንግግር ከሆነውና በብርሃን (ኑር) ከተሞላው መጽሐፍ ከቁርዓን ማግኘት የሚቻል ሲሆን የነቢዩን (ሰ.ዐ.ወ.) ትዕዛዛትና ክልከላዎች ደግሞ ሃያ ሶስት ዓመታት ከፈጀው ነቢያዊ የሕይወት ጉዞ መቅሰም ይቻላል፡፡

የዓለማቱ ጌታ አላህ ቁርዓንን ሊቀ መላእከት በሆነው በጂብሪል አማካይነት ለተከታታይ ሃያ ሶስት ዓመታት በነቢዩ ልብ ላይ አፍስሶታል፡፡ ይህም ማለት በሌላ አባባል የሌሎቹ ነቢያት የአምልኮት ዘይቤ፣አባባሎች ፣ ጠባይና ድርጊቶች ሁሉ በቁርዓን ተብራርተዋል ማለት ነው፡፡

በዚህ ሃቅ ማዕቀፍ ሥር እስከሆንን ድረስ ሁላችንም ነቢዩ ሙሐመድን (ሰ.ዐ.ወ.) ከነፍሳችን፣ ከንብረታችን፣ ከቤተሰባችንና ከማንኛውም ነገር አብልጠን መውደድ ይኖርብናል፡፡ እርሳቸውን መውደድ አላህን ለመውደድ የሚያበቃ እምነትን ያጎናጽፈናል፡፡ ይህም ማለት በሌላ አገላለጽ እርሳቸውን መውደድ አላህን መውደድና፣ አላህን መውደድ ደግሞ እርሳቸውን መውደድ ማለት ነውና፡፡

ይህ ቅድመ ሁኔታ ለመጨረሻው እስትንፋሳችን እንበቃ ዘንድ ወደዚያው የሚያደርሰን ዋነኛ ጎዳና ነው፡፡ ይህ ማለት የመጨረሻው እስትንፋሳችንን ሁኔታ የሚወስኑት ቀደም ብለን ስንምጋቸው የነበሩ እስትንፋሶቻችን ናቸው ማለት ነው፡፡ ለመጨረሻው እስትንፋሳችን ዝግጅት የሚጀመረው ነፍስ ካወቅንና የተከበሩት መዝጋቢ መላእክት በግራና በቀኝ ትከሻችን ላይ ሆነው እያንዳንዱን ድርጊታችንን መመዝገብ ከጀመሩባት ቅጽበት አንስቶ ነው፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ إِذْ يَتَلَقَّى ٱلْمُتَلَقِّيَانِ عَنِ ٱلْيَمِينِ وَعَنِ ٱلشِّمَالِ قَعِيدٌ ﴿١٧﴾ مَّا يَلْفِظُ مِن قَوْلٍ إِلَّا لَدَيْهِ رَقِيبٌ عَتِيدٌ ﴿١٨﴾ ﴾ ق: ١٧ - ١٨

‹‹ሁለቱ ቃል ተቀባዮች (መላእክት) ከቀኝና ከግራ ተቀማጮች በሚቀበሉ ጊዜ (አስታውስ)፡፡ ከቃል ምንም አይናገርም በአጠገቡ ተጠባባቂና ዝግጁ የሆኑ (መላእክት) ያሉበት ቢሆን እንጂ፡፡›› (ቃፍ፡17-18)

وَكُلَّ إِنسَٰنٍ أَلْزَمْنَٰهُ طَٰٓئِرَهُۥ فِى عُنُقِهِۦ ۖ وَنُخْرِجُ لَهُۥ يَوْمَ ٱلْقِيَٰمَةِ كِتَٰبًا يَلْقَىٰهُ مَنشُورًا ﴿١٣﴾ الإسراء: ١٣

‹‹ሰውንም ሁሉ በራሪውን (ሥራውን) በአንገቱ አስያዝነው፡፡ ለእርሱም በትንሣኤ ቀን የተዘረጋ ሆኖ የሚያገኘው የሆነን መጽሐፍ እናመጣለታለን፡፡ መጽሐፍህን አንብብ፤ ዛሬ ባንተ ላይ ተቆጣጣሪነት በነፍስህ በቃ (ይባላል)፡፡ (አል-ኢስራእ፡ 13 )

የአላህን ምርጥ ባሮች አላህንና መልእክተኛውን (ሰ.ዐ.ወ.) በመውደድና የእነርሱንም ትዕዛዛት ለመፈጸም ደፋ ቀና ሲሉ የኖሩ ናቸው፡፡ ይህም በመሆኑ በመጨረሻው የሕይወታቸው ፍጻሜ ትክክለኛዋን ከሊማ (ሸሃዳ) ከአንደበታቸው አውጥተው እስትንፋሳቸው ያቆማል፡፡ እንዲህ አይነት ሰዎችን በተመለከተ ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) የሚከተለውን የምሥራች ተናግረዋል፡-

‹‹የመጨረሻ ንግግሩ ከአላህ በስተቀር በሃቅ የሚያመልኩት ጌታ የለም፤ ሙሐመድም የአላህ መልእክተኛ ናቸው የሚል የሆነ ሰው ጀነት ይገባል፡፡›› (ሃኪም ሙስተድረክ ቅጽ.1 ቁ. 500)

በሌላ አባባል ሕይወቱን ሙሉ ይህን ከሊማ ከልቡ በማመን ሲደጋግመው የኖረ ሰው በመጨረሻው እስትንፋሱ ጊዜ ከአንደበቱ አውጥቶት መሞቱ አይቀርም፡፡ ይህ የዕድሜ ልክ መንፈሳዊ ጉዞ የሚጠይቃቸውን ማናቸውም መስዋእትነቶች ሁሉ ማሟላትን ግድ ይላል፡፡ የዚህ መልካም ንግግር (ከሊመቱ ጠይባ) ባለቤቶች እንዲሆኑ የሚመረጡት በምድር ዓለም ሕይወታቸው ከሥጋቸው ይልቅ ለመንፈሳቸው ያደሉ፣ ሃቅን የሚደግፉና ሃሰትን በጽናት የተፋለሙ የእውነት ሰዎች ናቸው፡፡ ከአላህ ሌላ የሆኑ አማልክት በሙሉ ጣኦታትና በሃሰት ትምህርቶች ላይ የተመሠረተ አምልኮት የሚፈጸምላቸው ናቸውና፡፡

በዓለማቱ ጌታ ኃያሉ አላህ የ ‹‹ሁን››ቃል የተገኘው ይህ አጽናፈ ዓለምና በውስጡ ያሉ ነገሮች፣ በይበልጥም ደግሞ የሰው ልጅ የሚገኝባት ይህች ዓለም አላፊ፣ ጠፊና በብልጭልጭ ትርዒቶች የተሞላች መሆኗን ማወቅ ተገቢ ነው፡፡

﴿ كُلُّ نَفۡسٖ ذَآئِقَةُ ٱلۡمَوۡتِۗ وَنَبۡلُوكُم بِٱلشَّرِّ وَٱلۡخَيۡرِ فِتۡنَةٗۖ وَإِلَيۡنَا تُرۡجَعُونَ ٣٥ ﴾
الأنبياء: ٣٥

‹‹ነፍስ ሁሉ ሞትን ቀማሽ ናት፡፡ ለመፈተንም በክፉም በበጎም እንሞክራችኋለን፡፡ ወደኛም ትመለሳላችሁ፡፡›› (አል-አንቢያ :35)

የሰው ልጅ ዋነኛ የመፈጠር ግብ መሆን ያለበት በመጪው ዓለም ለስኬቱ መብቃት ነው፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ حَقَّ تُقَاتِهِۦ وَلَا تَمُوتُنَّ إِلَّا وَأَنتُم مُّسۡلِمُونَ ١٠٢ ﴾ آل عمران: ١٠٢

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ አላህን ተገቢውን መጠንቀቅን ተጠቀንቀቁት፡፡ እናንተም ሙስሊሞች ሆናችሁ እንጂ አትሙቱ፡፡›› (አሊ-ዒምራን :102)

አላህ በተጨማሪም እንዲህ ይላል፡-

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ وَلۡتَنظُرۡ نَفۡسٞ مَّا قَدَّمَتۡ لِغَدٖۖ وَٱتَّقُواْ ٱللَّهَۚ إِنَّ ٱللَّهَ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ١٨ ﴾ الحشر: ١٨

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ፍሩ፡፡ ማንኛይቱም ነፍስ ለነገ ያስቀደመችውን ትመልከት፡፡ አላህንም ፍሩ፤ አላህ በምትሰሩት ሁሉ ውስጥ አዋቂ ነው፡፡ ›› (አል-ሐሽር፡ 18)

የሞት መከራ ይፍጠንም ይዘግይም መጪ ለመሆኑ ጥርጥር የለም፡፡ ይህን ሐቅ ወደድንም ጠላንም መቀበል ይኖርብናል፡፡ ሞት በቀንም ሆነ በሌሊት ከእኛ ጋር እንደተፋጠጠ ይገኛል፡፡ ሆኖም ግን የሰው ልጆች ስንባል ይህንን የማይቀር ፍዳ ለመቀበልና ለእርሱም ሁነኛ ዝግጅት ለማድረግ ብዙም ስንጥር አንታይም፡፡ ይህም ዝንጋቴያችን በመጨረሻ በራሳችን ላይ ልንገፈትረው የማንችል የሆነን መከራ ከመቆለል በስተቀር ሌላ ነገር አናተርፍም፡፡ እንደተዘናጋንም ሞት በድንገት ደርሶ እያካለበ ይወስደናል፡፡ ከዚያች ቅጽበት በኋላም በነፍስ ወከፍ በእያንዳንዳችን ላይ ቂያማ (ዕለተ ትንሳዔ) የቆመብን ያህል ይሆናል፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ ٱقۡتَرَبَ لِلنَّاسِ حِسَابُهُمۡ وَهُمۡ فِي غَفۡلَةٖ مُّعۡرِضُونَ ١ ﴾ الأنبياء: ١

‹‹ለሰዎች እነርሱ በዝንጋታ ውስጥ (መሰናዳትን) የተው ሆነው ሳሉ ምርመራቸው ቀረበ፡፡›› (አል-አንቢያ ፡ 1)

ኃያሉ አላህ መዘናጋት ለማንም እንደማይበጅና የሚያመጣው መዘዝም የከፋ መሆኑን እንዲህ በማለት ይገልጻል፡-

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلۡإِنسَٰنُ مَا غَرَّكَ بِرَبِّكَ ٱلۡكَرِيمِ ﴿٦﴾ ٱلَّذِي خَلَقَكَ فَسَوَّىٰكَ فَعَدَلَكَ ﴿٧﴾ فِيٓ أَيِّ صُورَةٖ مَّا شَآءَ رَكَّبَكَ ﴿٨﴾ ﴾ الانفطار: ٦ - ٨

‹‹አንተ ሰው ሆይ! በቸሩ ጌታህ ምን አታለለህ? በዚያ በፈጠረህ፣ አካለ ሙሉም ባደረገህ፣ ባስተካከለህም:: በማንኛውም በሻው ቅርጽ በገጣጠመህ (ጌታህ ምን አታለለህ? (አል-ኢንፊጣር፡ 6-8)

ሃቁና በዚህች ዓለም ላይ ያለው የሕይወት ተሞክሮ እንደሚያሳየን የሰው ልጅ በየእለቱ የመሞት እድሉ ከፍ ያለና ሕይወቱን የሚያሳጡት ነገሮችም ከጊዜ ወደ ጊዜ እየበረከቱ መሄዳቸውን ነው:: ህመም፣ ያልታሰበ አጋጣሚ፣ ሰው ሰራሽ አደጋ፣ የተፈጥሮ አደጋ፣ ጦርነት ወዘተ .. የሰውን ነፍስ ለመቀማት የተሰናዱ የተለያዩ ሰበቦች ናቸው::

ይሁን እንጂ ብዙ ሰዎች ይህን ከመሰለው አስፈሪ ሁኔታ ጋር ውለው እያደሩ የሞትን መምጣት ወይም አለመምጣት ከጉዳይ አይከቱትም:: ለመሆኑ ሞት ማለት በዚህችና በመጪው ዓለም መካከል የሚገኝና ሁለቱንም የሚለያይ መስመር መሆኑን ልብ አላሉምን? አላህ ይህን መሳይ ሁኔታ ውስጥ ለሚገኙ ሰዎች የሚከተለውን ተግሳጽ በቁርዓን ይሰጣል፡-

﴿ أَيَحۡسَبُ ٱلۡإِنسَٰنُ أَن يُتۡرَكَ سُدًى ﴿٣٦﴾ أَلَمۡ يَكُ نُطۡفَةٗ مِّن مَّنِيّٖ يُمۡنَىٰ ﴿٣٧﴾ ﴾ القيامة: ٣٦ - ٣٧

‹‹ሰው ስድ ሆኖ መትተውን ይጠረጥራልን? የሚፈሰስ ከሆነ የፍትወት ጠብታ አልነበረምን?›› (አል-ቂያማህ፡ 36-37)

የዓለማት ጌታ አላህ ይህችን ዓለምና በውስጧ የያዘቻቸውን ጉዳጉዶች ሁሉ እንዲሁም የሰውን ልጅ ሲፈጥረው ለታላቅ ዓላማ መሆኑንና ይህንንም የተፈጠረበትን ታላቅ ግብ ችላ ብሎ እንዳይገናኘው አላህ አበክሮ ያስጠነቅቃል፤ እንዲህ በማለት ፡-

﴿ وَمَا خَلَقۡتُ ٱلۡجِنَّ وَٱلۡإِنسَ إِلَّا لِيَعۡبُدُونِ ﴿٥٦﴾ ﴾ الذاريات: ٥٦

‹‹ጋኔንና ሰውንም ሊገዙኝ እንጅ ለሌላ አልፈጠርኳቸውም፡፡›› (አዝ-ዛሪያት፡ 56)

አላህ በተጨማሪም እንዲህ ይላል፡-

﴿ إِنَّ ٱلَّذِينَ لَا يَرۡجُونَ لِقَآءَنَا وَرَضُواْ بِٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَٱطۡمَأَنُّواْ بِهَا وَٱلَّذِينَ هُمۡ عَنۡ ءَايَٰتِنَا غَٰفِلُونَ ٧ أُوْلَٰٓئِكَ مَأۡوَىٰهُمُ ٱلنَّارُ بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ٨ ﴾ يونس: ٧ - ٨

‹‹እነዚያ መገናኘታችንን የማይፈሩት ቅርቢቱንም ሕይወት የወደዱ በእርሷም የረኩ እነዚያም እነርሱ ከአንቀጾቻችን ዘንጊዎች የሆኑ እነዚያ ይሠሩት በነበሩት ምክንያት መኖሪያቸው በእሳት ውስጥ ነው፡፡ ›› (ዩኑስ፡ 7-8)

ስለዚህ የሰው ልጆች ከላይ የተጠቀሱትን የቁርዓን አንቀፆች ሁልጊዜም በማስተንተን በእነርሱ እየተመሩ ምድራዊ ሕይወታቸውን ሊመሩ ግድ ነው፡፡ ደግመውና ደጋግመው ማስታወስ ያለባቸው በተሰጣቸው በህይወት የመቆየት እድል መልካም ሥራ ሠርተውና በበቂ ሁኔታ ተሰንቀው ወደ መጪው ዓለም መሄድ የሚያስፈልግ መሆኑን ነው፡፡ ሞት አንድ ጊዜ ከመጣና በእርሱ መዳፍ ውስጥ ከተጨመደዱ በኋላ መልካም ሥራን መሥራት ፈጽሞ የማይታሰብ ነገር ነውና፡፡ የጥበብና የማስተዋል ባለቤት የሆነው አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَأَنفِقُواْ مِن مَّا رَزَقۡنَٰكُم مِّن قَبۡلِ أَن يَأۡتِيَ أَحَدَكُمُ ٱلۡمَوۡتُ فَيَقُولَ رَبِّ لَوۡلَآ أَخَّرۡتَنِيٓ إِلَىٰٓ أَجَلٖ قَرِيبٖ فَأَصَّدَّقَ وَأَكُن مِّنَ ٱلصَّٰلِحِينَ ١٠ وَلَن يُؤَخِّرَ ٱللَّهُ نَفۡسًا إِذَا جَآءَ أَجَلُهَاۚ وَٱللَّهُ خَبِيرُۢ بِمَا تَعۡمَلُونَ ١١ ﴾ المنافقون: ١٠ - ١١

‹‹አንዳችሁም ሞት ሳይመጣውና ጌታዬ ሆይ! እንድመጸውትና ከደጋጎቹም ሰዎች እንድሆን ጥቂት ጊዜ ብታቆየኝ ኖሮ እመኛለሁ፤ ከማለቱ በፊት ከሰጠናችሁ ሲሳይ ለግሱ፡፡ ማንኛይቱም ነፍስ (የሞት)

ጊዜዋ በመጣባት ጊዜ አላህ በፍጹም አያቆያትም። አላህም በምትሠሩት ሁሉ ውስጥ አዋቂ ነው።›› (አል- ሙናፊቁን ፡ 10-11)

የሰው ልጆች መጨረሻቸው ከአፈር መለወስ፣ ብቸኝነት፣ አስፈሪ ዝምታን የሚያስከትለው ሞትና በቀብር መከተት መሆኑን ያውቃሉ። ይሁን እንጂ ብዙዎቹ ለዚህ - ከመልካም ሥራ በስተቀር ጥሩ አቀባበል የማይገኝበት ቦታ - ዝግጅት ሲያደርጉ አይታዩም። ሰዎች በእርግጥም የቀንና የምሽት መፈራረቅን እንደዘበት እያስተዋሉ በታላቅ መዘናጋት ውስጥ ይገኛሉ። በዚህች ዓለም ውጥንቅጡ የወጣ ሕይወት፣ በገንዘብ፣ በልጆችና በብልጭልጭ ነገሮች እየተፎካከሩ ይዋልላሉ። አጠቃላይ ሁኔታቸው በሚከተለው የቁርዓን አንቀጽ የተገለጸውን ይመስላል፡-

﴿أَلۡهَىٰكُمُ ٱلتَّكَاثُرُ ۝١ حَتَّىٰ زُرۡتُمُ ٱلۡمَقَابِرَ ۝٢ كَلَّا سَوۡفَ تَعۡلَمُونَ ۝٣ ثُمَّ كَلَّا سَوۡفَ تَعۡلَمُونَ ۝٤ كَلَّا لَوۡ تَعۡلَمُونَ عِلۡمَ ٱلۡيَقِينِ ۝٥﴾ التكاثر: ١ - ٥

‹‹በብዛት መፎካከር (ጌታችሁን ከመገዛት) አዘናጋችሁ። መቃብሮችን እስከጎበኛችሁ ድረስ። ተከልከሉ ወደፊት (ውጤቱን) ታውቃላችሁ። ከዚያም ተከልከሉ ወደፊት ታውቃላችሁ። በእውነቱ (የሚጠብቃችሁን) እርግጠኛ እውቀትን ብታውቁ ኖሮ (ባልዘነጋችሁ ነበር)።›› (አት-ተካሱር፡ 1-5)

እርግጥ ነው ከተወለድንበት ጊዜ ጀምሮ ሞተን ወደ መቃብራችን እስክንከተት ድረስ ብዙዎቻችን የምንኖረው ዘልማዳዊና ግዴለሽነትን የተላበሰ ሕይወት ነው። በዚህ ሂደትም ረዥሙን ጉዞ ከሚገባው በላይ የሚጓዝና በእድሜ ክርን ተደቁሶ ወደ ልጅነት ሕይወቱ የሚመለስ ሰው አለ። እንዲህ ዓይነቱ ሰው በቂ ስንቅ ይዞ ካልሄደ ወዮለት! የሚከተለው የቁርዓን አንቀጽ ይህንኑ ይገልጻል፡-

﴿وَمَن نُّعَمِّرۡهُ نُنَكِّسۡهُ فِي ٱلۡخَلۡقِۚ أَفَلَا يَعۡقِلُونَ ۝٦٨﴾ يس: ٦٨

‹‹ዕድሜውንም የምናረዝመውን ሰው በፍጥረቱ (ወደ ደካማነት) እንመልሰዋለን፡፡ አያውቁምን?›› (ያሲን፡ 68)

አቡ ሰፍዋን አብደላህ ቢን ቡስር አል-አስለሚ (ረ.ዐ.) ባስተላለፉትና ቲርሚዚ በዘገቡት ሐዲስ ፤ የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ብለዋል፡-

‹‹ከሰዎች ሁሉ በላጩ ዕድሜው ረዝሞ ሥራው ያማረ ሰው ነው፡፡››

የሕይወትን አቀበትና ቁልቁለት የበዛበት አድካሚ ጉዞ በመጨረስ ሰው ወደ መቃብሩ ከመግባቱና ‹‹ሩጫዬን ጨርሻለሁ›› ከማለቱ በፊት አሸናፊ የሚያደርገውን መንገድና የኑሮ ዘይቤ መምረጥ አለበት፡፡ ይኸውም በስጋዊ ስሜቶቹ ላይ ለመሠልጠንና በነፍስያውም ላይ ለመንገስ የሚያስችለው አላህን የመፍራት መንገድ ነው፡፡

አቡ ያዕላ ሽዳድ ኢብን አውስ (ረ.ዐ.) ነቢዩ እንዲህ ማለታቸውን ዘግበዋል፡-

‹‹አዋቂና ብልህ ሰው ማለት ሥጋዊ ፍላጐቱንና ስሜታዊ ዝንባሌውን ተቆጣጥሮ ከሞት በኋላ ላለው ሕይወቱ የሰራ ሰው ነው፡፡ ሞኝ፣ ተላላና ደካማ ሰው ማለት ደግሞ ራሱን (ወደተከለከሉና አጥፊ ወደሆኑ እኩይ ምግባራት በምትመራው ነፍሱ) ስሜታዊ ዝንባሌ ቁጥጥር ስር የዋለና የዝንባሌው ተከታይ በመሆን (የአላህን ምህረትና ፀጋን ያለ አንዳች ጥረት) የሚጠብቅ ነው፡፡ ›› (ቲርሚዚ የዘገቡት)

ከነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ) መላክ በፊት ኡካዝ  በተባለው የአረቢያ ዝነኛ የመገበያያ ሥፍራ  ኩሳ ቢን ሰዒዳህ የተባለ አላህን የሚፈራ ሰው እዚያ ለተሰበሰበው ሕዝብ የሚከተለውን ንግግር አድርጐ ነበር፡፡ ይህ ሰው በሕዝቦቹ ዘንድ የሚወደድና አክብሮት የተቸረው በመሆኑ ገና ወደ ሥፍራው እንደደረሰ ሞቅ ያለ አቀባበል ነበር የተደረገለት፡፡ እናም እንዲህ አለ፡-

‹‹ሰዎች ሆይ! ወደ እኔ ኑ፡፡ ከዚያም የምነግራችሁን አድምጡና ተግሳጽን ውሰዱ፡፡ ፍጥረት የተባለ ሁሉ ይሞታል፡፡ የሞተ ደግሞ ይበሰብስና ከአፈር ይደባለቃል፡፡ ዝናብ ይዘንባል፣ እጽዋትና ሳሮች ይበቅላሉ፡፡ ሕጻናት ይወለዱና አድገው ወላጆቻቸውን ይተካሉ፡፡ ከዚያም ሁሉም ነገር ያረጅና ያልቅለታል፡፡ ይህ ዓለም የክስተቶች ቅደም ተከተል እንጂ ሌላ አይደለም፡፡ አንዱ ሌላውን እየተከተለ የሚፈራረቅበት መድረክ…››

አቡ ሰኢድ አል-ኹድሪ (ረ.ዐ) ባስተላለፉት መሠረት የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ ብለዋል፡-

‹‹ዱንያ (ዓለም) አረንጓዴና ጣፋጭ ናት፡፡ አላህ በዚህች ዓለም ላይ ተጠሪው አድርጓችሁ ምን እንደምትሰሩ ያያችኋል፡፡ በዓለማዊ መጠቀሚያ ውስጥ ተዘፍቃችሁ ከመማረክና ከሴቶች ጋር በሚኖራችሁ ግንኙነት ከሚፈጠረው እኩይ ተግባር ተጠንቀቁ፡፡ አላህን ፍሩ፡፡ የእስራኢል ልጆች የመጀመሪያ መፈተኛ ሴቶች ነበሩና፡፡›› (ሙስሊም)

ዓሊ ኢብን አቡ ጧሊብ (ረ.ዐ.) እንዲህ ብለዋል፡-

‹‹የሰው ልጆች ሁሉ በእንቅልፍ ላይ ናቸው፡፡ ሲሞቱ ከእንቅልፋቸው ይነቃሉ፡፡ ››

ስለዚህም እውነተኛ ሕይወት ማለት ይህች ያለንባትና ፈጣን የሆነችው አይደለችም፡፡ እውነተኛዋ የመኖሪያ ሃገር አላህ ለፈራሀያን ደግሶ ያዘጋጃት የሆነችው የመዘውተሪያዋና መደሰቻዋ ጀነት ናት፡፡

﴿ وَسَارِعُوٓاْ إِلَىٰ مَغۡفِرَةٖ مِّن رَّبِّكُمۡ وَجَنَّةٍ عَرۡضُهَا ٱلسَّمَٰوَٰتُ وَٱلۡأَرۡضُ أُعِدَّتۡ لِلۡمُتَّقِينَ ١٣٣ ﴾ آل عمران: ١٣٣

‹‹ከጌታችሁ ወደሆነችም ምሕረትና ስፋቷ እንደ ሰማያትና ምድር ወደ ሆነች ገነት አላህን ለሚፈሩ የተዘጋጀች ስትሆን ተቻኮሉ፡፡›› (አሊ-ዒምራን፡ 133)

ከሞት ሁሉ አስቀያሚ የሆነው ሞት ከአላህ ጋር ሳይተዋወቁና እርሱንም ሳይገዙት መሞት ነው፡፡ ኃያሉ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ حَقَّ تُقَاتِهِۦ وَلَا تَمُوتُنَّ إِلَّا وَأَنتُم مُّسۡلِمُونَ ﴿١٠٢﴾ ﴾ آل عمران: ١٠٢

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ተገቢውን መጠንቀቅን ተጠንቀቁት፡፡ እናንተም ሙስሊሞች ሆናችሁ እንጂ አትሙቱ፡፡›› (አሊ-ዒምራን፡ 102)

ለዚህም ነው አማኝ የሆነ ሰው እንዴት እንደሚኖርና እንዴትም እንደሚሞት በማሰብ ሁልጊዜም መጨነቅ ያለበት፡፡ ሕይወቱም ሆነ አሟሟቱ አላህ በሚፈልገውና በሚወደው መንገድ መሆን ይኖርበታልና፡፡

﴿ قُلۡ إِنَّ صَلَاتِي وَنُسُكِي وَمَحۡيَايَ وَمَمَاتِي لِلَّهِ رَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿١٦٢﴾ لَا شَرِيكَ لَهُۥۖ وَبِذَٰلِكَ أُمِرۡتُ وَأَنَا۠ أَوَّلُ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ﴿١٦٣﴾ ﴾ الأنعام: ١٦٢ - ١٦٣

‹‹ስግደቴም፣ መገዛቴም፣ ሕይወቴም፣ ሞቴም ለዓለማት ጌታ ለአላህ ነው በል፡፡ ለእርሱ ተጋሪ የለውም፡፡ በዚህም (በማጥራት) ታዘዝኩ፡፡...›› (አል-አንአም፡ 162-163)

ይህን ከማድረግና ቀናውን ጉዳና ከመከተል ውጪ ለማንም ሰው ቢሆን ነቢያትን ጨምሮ መድህን የሚያስገኝ ነገር አይኖርም፡፡

በዚህም የተነሳ ነው የአላህ ነቢይ ዩሱፍ (ዐ.ሰ.) ወደ አላህ በመጠጋት የእርሱን እርዳታና ጥበቃ እንደሚሹ ሲገልጹ የምናያቸው፡፡ ያለ እርሱም እዝነትና ድጋፍ ሙስሊም ሆኖ መሞት የማይቻል ነውና፡፡

﴿ رَبِّ قَدۡ ءَاتَيۡتَنِي مِنَ ٱلۡمُلۡكِ وَعَلَّمۡتَنِي مِن تَأۡوِيلِ ٱلۡأَحَادِيثِۚ فَاطِرَ ٱلسَّمَٰوَٰتِ وَٱلۡأَرۡضِ أَنتَ وَلِيِّۦ فِي ٱلدُّنۡيَا وَٱلۡأٓخِرَةِۖ تَوَفَّنِي مُسۡلِمٗا وَأَلۡحِقۡنِي بِٱلصَّٰلِحِينَ ﴿١٠١﴾ ﴾ يوسف: ١٠١

‹‹ጌታዬ ሆይ! ከንግሥና በእርግጥ ሰጠኸኝ፡፡ ከሕልሞችም ፍቺ አስተማርከኝ፡፡ የሰማያትና የምድር ፈጣሪ ሆይ! አንተ በቅርቢቱና በመጨረሻይቱ ዓለም ረዳቴ ነህ፡፡ ሙስሊም ሆኜ ግደለኝ፡፡ ከመልካሞቹም አስጠጋኝ (አለ)፡፡ ››(ዩሱፍ፡101)

ይህን የቁርአን አንቀጽ ስናነብ ግልጽ የሚሆንልን ጉዳይ ነቢያትም ቢሆኑ የአላህ እዝነትና ርህራሄ ካልተከተላቸው በስተቀር ለስኬት እንደማይበቁ ነው፡፡ እነርሱ እንዲህ አላህን የሚፈሩና ለፍጻሜያቸው የሚያስቡ ከሆኑ እኛ እንዴት ልንሆን ነው? ስለዚህ ማንኛውም ሙስሊም የሆነ ሰው ሕይወቱን መምራት ያለበት አላህን በመፍራትና ምህረቱንም ተስፋ በማድረግ መሆን ይኖርበታል፡፡

በፍርዱ ቀን የምናየው ሁኔታ በዚህች ዓለም የመጨረሻዋን እስትንፋሳችን የነበረንን ሁኔታና ያሳለፍነውን የሕይወት ዘይቤ ነው በቀጥታ የሚያንፀባርቀው፡፡ የእኛ የሙስሊሞች መድህን የተረጋገጠበት የሆነው ቁርአን፤ ሰዎች በመጨረሻው የሕይወታቸው ቅጽበት ያሳዩትን ሁኔታና ምድራዊ አኗኗራቸው ምን ይመስል እንደነበር እያነፃፀረ ብዙ ምሳሌዎችን አቅርቦልናል፡፡

ለምሳሌ፡ ነቢዩላህ ሙሳ (ዐ.ሰ) ከፈጣሪያቸው የተሰጣቸውን ተዓምር ለፈርዖንና መማክርቱ እንዲሁም እርሱ ለሰበሰባቸው አስማተኞች ባሳዩ ጊዜ የተከሰተው ምን ነበር? አዎን! ጠንቋዮቹ በሙሳ ጌታ ማመናቸውን በመግለጽ በስግደት ወድቀዋል፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ قَالُوٓاْ ءَامَنَّا بِرَبِّ ٱلۡعَٰلَمِينَ ﴿١٢١﴾ رَبِّ مُوسَىٰ وَهَٰرُونَ ﴿١٢٢﴾ ﴾ الأعراف: ١٢١ - ١٢٢

‹‹አሉ…በዓለማት ጌታ አመንን፡፡ በሙሳና በሃሩን ጌታ፡፡›› (አል-አዕራፍ፡ 121-122)

ይሁን እንጂ ጨካኙና አመለኛው ፈርኦን በሥጋቸው ብቻ ሳይሆን በነፍሳቸውም ላይ ስልጣን ያለው እስኪመስለው ድረስ በመደንፋት እንዲህ እያለ አስፈራርቷቸዋል፡-

﴿ قَالَ فِرۡعَوۡنُ ءَامَنتُم بِهِۦ قَبۡلَ أَنۡ ءَاذَنَ لَكُمۡۖ إِنَّ هَٰذَا لَمَكۡرٞ مَّكَرۡتُمُوهُ فِي ٱلۡمَدِينَةِ لِتُخۡرِجُواْ
مِنۡهَآ أَهۡلَهَاۖ فَسَوۡفَ تَعۡلَمُونَ ١٢٣ لَأُقَطِّعَنَّ أَيۡدِيَكُمۡ وَأَرۡجُلَكُم مِّنۡ خِلَٰفٖ ثُمَّ لَأُصَلِّبَنَّكُمۡ
أَجۡمَعِينَ ١٢٤ ﴾ الأعراف: ١٢٣ - ١٢٤

‹‹ፈርኦን አለ፡- እኔ ለእናንተ ሳልፈቅድላችሁ በፊት በእርሱ አመናችሁን? ይህ በከተማይቱ ውስጥ ሰዎችን ከርሱ ለማውጣት በእርግጥ የተስማማችሁበት ተንኮል ነው፡፡ ወደፊትም (የሚደርስባችሁን) ታውቃላችሁ፡፡ እጆቻችሁንና እግሮቻችሁን በማፈራረቅ በእርግጥ እቆራርጣለሁ፡፡ ከዚያም ሁላችሁንም በእርግጥ እሰቅላችኋለሁ፡፡ ›› (አል-አዕራፍ ፡123-124)

ሆኖም ግን ፈርዖን እንዲህ ብሎ ቢያስፈራራቸውም ቅሉ በእምነት ውስጣቸው የረሰረሰው አማኞች በጥልቅ ዕምነት በተጥለቀለቀ ወኔ እንዲህ አሉት ፡-

﴿ قَالُوٓاْ إِنَّآ إِلَىٰ رَبِّنَا مُنقَلِبُونَ ١٢٥ وَمَا تَنقِمُ مِنَّآ إِلَّآ أَنۡ ءَامَنَّا بِـَٔايَٰتِ رَبِّنَا لَمَّا جَآءَتۡنَاۚ
رَبَّنَآ أَفۡرِغۡ عَلَيۡنَا صَبۡرٗا وَتَوَفَّنَا مُسۡلِمِينَ ١٢٦ ﴾ الأعراف: ١٢٥ - ١٢٦

‹‹...አሉ፡፡ እኛ ወደ ጌታችን ተመላሾች ነን፡፡ የጌታችንም ተአምራቶች በመጡልን ጊዜ ማመናችንን እንጂ ከእኛ ሌላ የምትጠላው ነገር የለም፡፡ ጌታችን ሆይ ፤ በእኛ ላይ ትዕግስትን አፍስስ፡፡ ሙስሊሞችም ሆነን ግደለን፡፡ ›› (አል-አዕራፍ፡ 125-126)

ይህን ካሉ በኋላ በታላቅ ድፍረት ፈርዖንን ሊጋፈጡት ተዘጋጁ፡፡ እስቲ የእነዚህን ሰዎች ሁኔታ በጽሞና እናስተውል፡፡ ፈርዖን እንደዛተው ግፉን በእነርሱ ላይ መፈጸም ቢጀምርም ወደ ኋላ ከማፈግፈግና ነፍሳቸውንና አካላቸውን አትርፈው የቅርቢቱን ሕይወት ከመሻት ይልቅ ሙስሊሞች ሆነው መሞትን ብቻ ከጀሉ፡፡ በዚያ ታላቅ ጽናትን በሚጠይቅ መሪር ሰዓት የጌታቸውን እገዛ በመሻት

‹‹…ጌታችን ሆይ! በእኛ ላይ ትዕግስትን አፍስስ፡፡ ሙስሊሞችም ሆነን ግደለን፡፡›› አሉ፡፡

ይህን ታላቅ እምነታቸውን ጠብቀው ከዚህች ዓለም ለመሰናበት እጆቻቸውንና እግሮቻቸውን መቆረጥ እንዲሁም በስቅላት ተቀጥተው የመሞትን ዋጋ አስከፍሏቸዋል፡፡ ምንም እንኳን አሟሟታቸው የሰማዕት (ሸሂድ) አሟሟት ቢሆንም፡፡

በተመሳሳይ ሁኔታ አሰሃቡል-ኡኽዱድ (የጉድጓዱ ባለቤቶች) እየተባሉ የሚጠሩት በየመን አካባቢ የነበሩ የአሃዳዊ ክርስትና ወይም በኢሣ መልእክተኝነት ያምኑ የነበሩ ሰዎች የከፈሉትን መስዋእትነት እናገኛለን፡፡ እነዚህ ሰዎች የአላህን አንድነትና የኢሣንም መልእክተኝነት ከመመስከርና የጣኦት አምልኮትን ከመቃወማቸው ውጪ የሠሩት ኃጢአት አልነበረም፡፡ ሆኖም ግን ጨካኝ በነበረው የሂሚዮር ንጉሥ ዘነዋስና በተከታዩቹ ታላቅ የሆነ ግፍ ተፈፀመባቸው፡፡ በየመንገዱ ዳርና ዳር በተቆፈሩ ጉድጓዶች ውስጥ በተነደደና በሚንቀለቀል እሳት ውስጥ ከነሕይወታቸው እንዲገቡ ተደርገዋል፡፡

ሐቢቡ ነጃር በመባል በቁርዓን ሱረቱ ያሲን ላይ የተጠቀሰው የአስሃቡል ቀርያ (የመንደሩ ሰዎች) ነዋሪ፣ ሲሆን በአላህ በማመኑ በድንጋይ ተወግሮ እንዲሞት ተደርጓል፡፡ ከመሞቱና ነፍሱ ከመውጣቷ በፊት ግን የዚህ ዓለም መስኮት ተዘግቶ የመጪው ዓለም ሕይወት መስኮት ከተከፈተለት በኋላ ትእይንት እንዲያይ ተደርጎ ነበር፡፡ በዚያም ታላቅ የሆነውን መለኮታዊ ፀጋና ማለቂያ የሌለውን የመጪውን ዓለም ተድላ አስተዋለ፡፡ ከዚያም በሕዝቦቹ አለማወቅና በመንፈስ መታወራቸውን በማሰብ በቁጭት እንዲህ አለ፡-

﴿ قِيلَ ٱدۡخُلِ ٱلۡجَنَّةَۖ قَالَ يَٰلَيۡتَ قَوۡمِي يَعۡلَمُونَ ﴿٢٦﴾ بِمَا غَفَرَ لِي رَبِّي وَجَعَلَنِي مِنَ ٱلۡمُكۡرَمِينَ ﴿٢٧﴾ ﴾ يس: ٢٦ - ٢٧

‹‹… ግባ ተባለ (እርሱም) አለ፤ ወገኖቼ ቢያውቁ እመኛለሁ፡፡ ጌታዬ ለእኔ ምህረትን ያደረገልኝና ከተከበሩትም ያደረገኝ መሆኑን፡፡›› (ያሲን ፡26-27)

በክርስትና የመጀመሪያ ዘመን አሃዳዊ ክርስትና እያበበ የነበረ ቢሆንም የግሪክና ሮማ ጣኦት አምላኪዎች ንጹህ የሆነውን ተውሂድ ይዘው ኢሳን በነቢይነት በተቀበሉ አማኞች ላይ ብዙ ግፎችን ይፈጽሙባቸው ነበር፡፡ ከግፎቻቸው መካከል ዋነኛው በቁማቸው (ከነሕይወታቸው) ለአንበሳና ለነብር አሳልፈው ይሰጧቸው የነበረው ነው፡፡ ሆኖም ግን እነዚያ ጠንካራ አማኞች በመከራ በመበርገግ እምነታቸውን እየካዱ ወደኋላ አላፈገፈጉም፡፡ ከዚያ ይልቅ ጽናትን በመላበስና የመጪውን ዓለም ሽልማት በማስታወስ ሁኔታውን ተጋፈጡት እንጂ፡፡

የአላህ አልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) በካዕባ ጥላ ሥር መጎናጸፊያቸውን ተንተርሰው ሳሉ፡- ‹‹ከአላህ እርዳታ ለምን አይጠይቁልንም? ለምንስ አይጸልዩልንም? ብለን ስሞታ አቀረብን፤ ነብዩም፡-

‹‹ከእናንተ በፊት ባለፉት ሕዝቦች ዘመን አንድ (አማኝ) ሰው ይያዝና ጉድጓድ ተቆፍሮለት ከጉድጓድ እንዲገባ ይደረጋል፡፡ ከዚያም መጋዝ ይመጣና ከራሱ ላይ ተደርጎ ለሁለት ይሰነጠቃል፡፡ ሥጋው ከአጥንቱ በብረት ሚዶዎች ይላጋል፡፡ ይህ ሁሉ ግን ከኃይማኖቱ አይመልሰውም ነበር፡፡…..››ማለታቸውን አቡ አብደላህ ኸባብ ኢብን አረት (ረ.ዐ) አስተላልፈዋል፡፡ (ቡኻሪ)

የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) የአብዱላህ ኢብን ኡመርን (ረ.ዐ.) ትከሻ ያዝ አድርገው እንዲህ ብለውት ነበር፡-

‹‹በዚህች ዓለም ላይ ስትኖር እንደ እንግዳ ወይም መንገድ አቋራጭ ሁን፡፡››

ከዚያም በኋላ ኢብን ኡመር (ረ.ዐ.) ራሳቸው እንዲህ ይሉ ነበር፡-

‹‹ካመሸህ ንጋትን አትጠብቅ፤ በንጋት ደግሞ እስከምሽቱ (እኖራለሁ ብለህ) አትጠብቅ፡፡ ከጤናህ ለሕመምህ፤ ከሕይወትህ ደግሞ ለሞትህ ተዘጋጅ፡፡›› (ቡኻሪ)

እነዚህ ከላይ በተከታታይ የተጠቀሱ ድንቅ አባባሎች የዚህችን ዓለም ሕይወት አጭር መሆን እንድናስታውስና ለእውነተኛው ሃገር (ለአኺራ) እንድንዘጋጅ ያደርጉናል፡፡ የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) በአንድ ወቅት በሶላታቸው ላይ እንዲህ ሲሉ ተደምጠዋል፡-

‹‹አላህ ሆይ ! ኑሮ ማለት የመጪው ዓለም (አኺራ) ኑሮ ነው ….›› (ቡኻሪ)

የመልእክተኛው (ሰ.ዐ.ወ.) ባልደረባዎች ይህንን እውነታ በሚገባ በመገንዘባቸው ታላቅ የሚባሉና ሕያው ሆነው የሚኖሩ ተምሳሌቶችን ትተው ለማለፍ በቅተዋል፡፡

ለምሳሌ ሁበይብ (ረ.ዐ.) ሲገደል፤ ወደ ተንዓም ሜዳ ከተወሰደ በኋላ በመገደያው ቦታ ላይ ሆኖ ለአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) ሰላምታ ለማድረስ በጣም ፈለገ፡፡ ሆኖም በዙሪያው ከተሰበሰቡት ከሃዲያን ውስጥ ይህን አደራ ተቀብሎ ሊያደርስለት የሚችል አንድም ሰው አልነበረም፡፡ ምርጫ ያልነበረው ሁበይብ (ረ.ዐ.) አይኖቹን ወደ ሰማይ ካቀና በኋላ እንዲህ አለ፡-

‹‹አላህ ሆይ! እዚህ ካሉት ሰዎች ውስጥ ለመልእክተኛህ ሰላምታዬን የሚያደርስልኝ ሰው አላገኘሁም፡፡ እባክህ አንተ ሰላምታዬን አድርስልኝ!›› በዚያው ቅጽበት ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) መዲና ሆነውና ከተከታዮቻቸው ጋር ተቀምጠው ሳሉ ‹‹ወአለይሂ ሰላም›› አሉ፡፡ ይህም ማለት ‹‹በእርሱም ላይ የአላህ ሰላም ይሁን›› ማለት ነው፡፡ ይህን የሰሙት ተከታዮቻቸው፡-

‹‹የአላህ መልእክተኛ ሆይ! ለማን ሰላምታ ነው አጸፋውን የመለሱት?›› በማለት ጠየቋቸው፡፡ እርሳቸውም ፡- ‹‹የወንድማችሁን

የሁበይብን ሰላምታ›› በማለት መልስ ሰጡ፡፡ ከዚያ በኋላ ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) ስለ ሁበይብ (ረ.ዐ) ሲናገሩ ‹‹በጀነት ጕረቤቴ ይሆናል፡፡›› ብለዋል፡፡

ሌላው በምሳሌነት ሊጠቀስ የሚችልና ለነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) ጥልቅ ፍቅር የነበረው ሰዓድ ኢብን ረቢአ (ረ.ዐ.) ነበር፡፡ ሳዕድ (ረ.ዐ.) ነቢዩን (ሰ.ዐ.ወ.) በማማከር የተሳካለት ሰው ነበር፡፡ በተለይም የጦር ስልትን በተመለከተ ብዙ ምክርን ለግሷቸዋል፡፡ በኡሁድ ውሎ የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) በውጊያ ላይ የቆሰሉና የተሰው (ሸሂድ የሆኑ) ሰዎች ተለይተው እንዲታወቁ ትዕዛዝ ሰጡ፡፡ በተለይ ደግሞ ሳዕድ ኢብን አል-ረቢአ ምን እንዳጋጠመው ለማወቅ የተለየ ጉጉት አሳዩ፡፡ ከዚያም አንድ ባልደረባቸውን ወደ ውጊያው ሜዳ ሄዶ የሳዕድን (ረ.ዐ.) ሁኔታ አጣርቶ እንዲያመጣ ላኩት፡፡ ያ መልእክተኛ ሳዕድን ለማግኘት ብዙ ደከመ፡፡ በሕይወት ካለ ጥሪዬን ይሰማል ብሎ በማሰብም እየጮኸ ተጣራ፡፡ ሆኖም ግን የሳዕድ ሬሳ አልተገኘም፡፡ በመጨረሻ ብዙም ተስፋ ሳያደርግ በሞቱትና በቆሰሉት ሰዎች መካከል ሰዓድን (ረ.ዐ.) ሊፈልገው ተንቀሳቀሰ፡፡ በድኑ ቆስሎ በሞትና በሕይወት መካከል ሆኖ አገኘው፡፡ ከዚያም እንዲህ አለው፡- ‹‹ሳዕድ ሆይ! ነቢዩ ናቸው አንተን እንድፈልግ የላኩኝ፡፡ በሕይወት መኖርህን ወይም ሰማእት መሆንህን እንዳጣራ ፈልገዋል፡፡›› ሰዓድ በዚህን ጊዜ ያለ የሌለ ጉልበቱን ሁሉ አሰባስቦ ድክም ባለ ድምጽ እንዲህ አለ፡-

‹‹እኔ አሁን በሕይወት ካሉት ሳይሆን ከሞቱት ቁጥር ነኝ፡፡ ከዚያም እንዲህ በማለት ንግግሩን አከለ፡- ‹‹ለአላህ መልእክተኛ ሰላምታየን አድርስልኝ፡፡ ለሕዝባችን (ለአንሷሮች) ለዋሉት ውለታ አላህ ምንዳቸውን ይክፈላቸው፡፡ በአላህ ይሁንብኝ ከእናንተ አንዳችሁ ዓይናችሁ እያየና በሕይወት እያላችሁ በአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) ላይ አንዳች ጉዳት ቢደርስ ከአላህ ዘንድ ይቅርታን አታገኙም፡፡›› ይህን ካለ በኋላ ሰዓድ ነፍሱ ከአካሉ ተለየች፡፡ አላህ ይዘንለት፡፡ ሥራውንም ይውደድለት፡፡ የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) የሰዓድ (ረ.ዐ.) ሁኔታ ሲነገራቸው እንዲህ

አሉ፡- ‹‹በእርሱም ላይ የአላህ ሰላም ይውረድበት፤ በሕይወቱም ሳለ በሚሞትበትም ጊዜ የአላህን መልእክተኛ በምክሩ ረድቷል፡፡››

የሚቀጥለው ዘገባ ደግሞ ከሁዘይፋ (ረ.ዐ.) የተወራ ሲሆን የነቢዩን (ሰ.ዐ.ወ.) ባልደረቦች የሞራልና የስብዕና ምጥቀት ያሳያል፡፡

‹‹በየርሙክ ዘመቻ ላይ ተገኝቸ ነበር፡፡ ውጊያው በኃይል ተፋፍሞ ከቆየ በኋላ በረድ ብሎ ነበር፡፡ ከሙስሊሞች ውስጥ የተወሰኑት በቀስትና በጦር በመወጋታቸው ቆስለው እዚህም እዚያም ወድቀው እያቃሰቱ መጨረሻቸውን ይጠባበቃሉ፡፡ የቀረኝን ጥንካሬ ሁሉ አስተባብሬ የአጎቴን ልጅ ለማፈላለግ በቆሰሉት ተዋጊዎች መካከል ስዘዋወር ከቁስለኞች መካከል በደም ኩሬ ውስጥ ተኝቶ አገኘሁት፡፡ በዚያ ሁኔታ ላይ እያለም መናገር ስላልቻለ በዓይኖቹ ነበር የሚያናግረኝ፡፡ እኔም የውሃ ኮሮጆዬን እያሳየሁት ውሃ ይፈልግ እንደሆነ በማለት፤ ‹‹ውሃ ትፈልጋለህ?›› አልኩት፡፡ ምንም ጥርጥር የለውም፡፡ የደረቁት ከንፈሮቹ ውሃ እንደሚያስፈልገው ይመሰክሩ ነበር፡፡ ይሁን እንጂ ይህንኑም ቢሆን ለመመለስ አቅም አልነበረውም፡፡ አይኖቹን ወዲያና ወዲህ በማንከባለል ያለበትን የስቃይ ሁኔታ ሊገልጽልኝ ይሞክር ነበር፡፡ ውሃውን እየሰጠሁት እያለሁ የኢክሪማ ድምጽ ተሰማ ‹‹ውሃ ፣ ውሃ፣ እባካችሁ ማን ነው ውሃ የሚሰጠኝ?›› አለ፡፡ ይህን ድምጽ እንደሰማ የአጎቴ ልጅ ሃሪስ ውሃውን ለኢክሪማ እንድሰጠው በአይኖቹ ገለጸልኝ፡፡

እኔም ሸሂድ (ሰማእት) ሆነው በተኳሳው አሸዋ ላይ በተጋደሙት አስከሬኖች መካከል እየሮጥኩ ወደ ኢክሪማ ደርሼ ውሃውን ልሰጠው ስል የአያሽን ‹‹እባካችሁ ጠብታ ውሃ የለም?›› የሚል ድምጽ ሰማን፡፡ በዚህ ጊዜ ኢክሪማ ለአያሽ ውሃውን እንድወስድለት ነገረኝ፡፡ ልክ ሃሪስ ፈልጐ እንዳላገኘ ሁሉ ኢክሪማም ሳይጠጣ ቀረ፡፡ እኔም ጊዜ ሳላጠፋ በሙታኑ መካከል እየሮጥኩ አያሽ ጋር ስደርስ የሚከተሉትን ቃላቶች ከአንደበቱ ሰማሁ፡-

‹‹አላህ ሆይ! በአንተ መንገድ ነፍሳችንን ለመሰዋት አንድም ጊዜ ወደኋላ ብለን አናውቅም፡፡ እባክህ የሸሂድነትን ክብር አጐናጽፈን፤

ኃጢአታችንንም ማረን!›› እያሸ እያበቃለት ነበር፡፡ ውሃውን ተመለከተው፡ ፡ ሆኖም ግን ለመጠጣት ጊዜ አልነበረውም፡፡ የመጨረሻ ንግግሩ ሸሃዳ ማለት ነበር፡፡ ከዚያም ፈጥኜ ወደ ኢክሪማ ስሄድ እርሱም ሰማእት ሆኖ አገኘሁት፡፡ በዚህ ጊዜ ‹‹አሁን ግን ለአጎቴ ልጅ ልደርስለት ይገባል›› ብዬ በፍጥነት ወደ ሃሪስ ስሄድ ያሳዝናል፣ እርሱም የጓደኞቹን እጣ ተጋርቷል፡፡ በሚያሳዝን ሁኔታ የውሃ ኮሮጆዬ እንደሞላ ቢሆንም እነዚያ ሶስት ሰማዕታት (ሸሂዶች) ሳይቀምሱለት ነበር ነፍሶቻቸው ከሥጋቸው የተለዩት፡፡

ሁዘይፋ (ረ.ዐ.) በዚያ ቦታ ላይ ያን ክስተት ካስተዋለ በኋላ ምን እንደተሰማው ሲናገር እንዲህ ይላል፡-

‹‹በሕይወቴ ሁሉ ብዙ አጋጣሚዎችን ተመልክቻለሁ፡፡ ነገር ግን እንደዚህ ክስተት መንፈሴን የናጠኝ አጋጣሚ አልተፈጠረም፡፡ በእነዚያ ሶስት ሰዎች መካከል ምንም ዓይነት የዝምድና ትስስር ባይኖርም አንዱ ለሌላው ያሳየውን አሳቢነት፣ ፍቅርና መስዋእትነት ሳስተውል እንዳደንቃቸው አድርጎኛል፡፡ ትዝታቸውም እስክሞት ድረስ በሕሊናዬ አብሮኝ ይኖራል፡፡

## ምዕራፍ ሁለት

# አላህን ማስታወስ

በዚህች ዓለም ላይ ቀናውን ጎዳና እንደተመራ (ሷሊህ) ሰው መኖር ካለብን ለመጪው ዓለም ስኬት ያበቃን ዘንድ በመልካም ሁኔታ ስንቃችንን ልንቋጥር ግድ ነው፡፡ በቀጣዩ ሐዲስ እንደተጠቀሰውም ሰው የዘራውን እንጂ ሌላን ነገር አያጭድም፡፡ ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) እንዲህ ብለዋል፡-

‹‹እንደ አኗኗራችሁ ትሞታላችሁ፡፡ እንደ አሟሟታችሁ ትቀሰቀሳላችሁ፡፡››

ዋናውና የመጨረሻው ግባችን መሆን ያለበት የመጨረሻውን ትንፋሻችንን ስናወጣ አላህ ዘንድ የሚኖረን አቀባበል ያማረ መሆኑን ማረጋገጥ ነው፡፡ ይህን ሁኔታ በአንክሮ ካስተነተንነው መለኮታዊው ምስጢር ብዙ ነገሮችን ያካተተ ሆኖ እናገኘዋለን፡፡ አንድ አማኝ ሕይወቱን በሙሉ መልካም ነገሮችን ሲፈጽም ቢኖርም ውድ የሆነችውን ጀነት በእርግጠኝነት ለማግኘት ሙሉ ዋስትና የለውም፡፡ በሌላ በኩል አንድ ሰው በኃጢአት ተዘፍቆ ቢኖር እንኳ የአላህን ምህረት ሊያገኝና በመጨረሻ ለስኬት ሊበቃ ይችላል፡፡ ይህን ጉዳይ አስመልክቶ ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) የሚከተለውን ሐዲስ ተናግረዋል፡-

‹‹…ከእርሱ በቀር ሌላ ጌታ በሌለው በአላህ ስም እምላለሁ፡፡ ከእናንተ አንዳችሁ የገነት ሰዎችን ሥራ የሚሰራ (የሚመስል) በእርሱና በእርሷ (በጀነት) መካከል የክንድ ያህል ርቀት እስኪቀር ድረስ፤ ነገር ግን የተጻፈው ይቀድመውና የጀሃነም ሰዎች የሚሰሩትን ሰርቶ ጀሃነም ይገባል፡፡ እንዲሁም ከመካከላችሁ የእሳት ሰዎች የሚሰሩትን የሚፈጽም (የሚመስል) አለ፡፡ ግና የተጻፈው ይቀድመውና የጀነት ሰዎች የሚሰሩትን ሥራ በመሥራት ጀነት ይገባል፡፡›› (ቡኻሪና ሙስሊም)

ከአላህ ፍጡራን ውስጥ እውቀትን የታደሉ፣ ሆኖም ግን በዚያ በተሰጡት እውቀት መንፈሳቸውን አስጊጠው የአላህን ሞገስ ከማግኘት ይልቅ ስሜታቸውን በመከተላቸው ምክንያት የከሰሩ ይገኛሉ፡፡ ከእነዚህ የክስረቱ ባለቤቶች መካከል ሰይጣን፣ ቃሩን ባዕላም ቢን በዉራ እንዲሁም የነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) የቅርብ ባልደረባ የነበረው ሳዕለባ ይገኙበታል፡፡ እነዚህ ሁሉ በቅርቢቱ ዓለም ሕይወት የተታለሉና ከአላህ እዝነት የተባረሩ መሆናቸው ይታወቃል፡፡

ሁላችንም እንደምናውቀው ሰይጣን በአንድ ወቅት በአላህ ዘንድ የከበረና ቀራቢ ባለሟልም ነበር፡፡ ሆኖም ግን በውስጡ ባሳደረው ኩራት የተነሣ የአላህን ታላቅነትና የሻውን እንደሚሰራ ማየትና መመዘን አልቻለም፡፡ እናም ከአቅሙ በላይ አላህን በመገዳደር የሰው ልጆች ሁሉ አባት ከሆኑት ከአደም እንደሚበልጥ ተናገረ፡፡ በዚሁ ትእቢቱም እየገፋበት መጥቶ የአላህን ትዕዛዝ ወደ መጣሱ ተሸጋገረ፡፡ በመጨረሻም ከአላህ እዝነት በመባረርና እስከፍርዱም ቀን ድረስ የእርሱን እርግማን በላዩ በመሸከም ሲባዝን ይኖራል፡፡ የፍርዱ ቀን ሲመጣም ወደ ዘላለማዊው ጀሃነም ከነዘርማንዘሮቹ ይገባል፡፡

ቃሩን በአንድ ወቅት ድሃ የነበረ ሲሆን አላህን የሚገዛ (ሷሊህ) ሰው ነበር፡፡ እንዲሁም የተውራት ዕውቀት ካላቸው ካህናትም ታላቁ ነበር፡፡ ከዚህም በላይ ሙሣ (ዐ.ሰ.) ባደረጉለት ጸሎት ምክንያት ሃብት የሚያስገኝ የኬሚስትሪ (አልኬሚ) ምስጢርን ያውቅ ነበር፡፡ ይሁን እንጂ ኋላ ኋላ ይህንን እውቀቱን ለከንቱና ተራ ፍላጐቱ ማዋል ጀመረ፡፡

የቃሩን ሃብት እጅግ ብዙ ከመሆኑ የተነሣ የካዝናዎቹን ቁልፎች ለመሸከም ብቻ ብዙ ሰዎች ያስፈልጉ ነበር፡፡

በዚህ ዓይነት ታላቅ ኩራትና ማንአለብኝነት የተወጠረው ቃሩን በአንድ ወቅት ነቢዩ ሙሣ (ዐ.ሰ.) ከገንዘቡ ዘካ አውጥቶ እንዲያካፍል ሲጠይቁት፡- ‹‹በገንዘቤ የምታዘው አንተ ነህ እንዴ?›› በማለት መለሰላቸው፡፡

በሌላ በኩልም ቃሩን ነቢዩ ሙሣ (ዐ.ሰ.) እና ወንድማቸው ሃሩን (ዐ.ሰ.) በያዙት መንፈሳዊ ደረጃም ይቀና ነበር፡፡ ይህ ቅናቱ የመጨረሻ ደረጃ ደርሶም ነቢዩ ሙሣን (ዐ.ሰ.) በብልግና ተጠያቂ እንደሆኑ በማስመሰል ከሷቸው ነበር፡፡ በዚህና በሌሎችም ቅጥ ያጡ ድፍረቶቹ አላህ ቃሩንን ከነሃብቱ በመሬት እንዲዋጥ  በማድረግ ቀጥቶታል፡፡

ባዕላም ቢን ባውራ የአላህን ልዩ ስም የሚያውቅና አላህን ከሚፈሩ የነገደ እስራኤል ሰዎች አንዱ ነበር፡፡ በወገኖቹ እስራኤላውያንም ዘንድ እንደ ቅዱስና ታላቅ ምሁር የሚቆጠር ነበር፡፡ ሆኖም ግን ባዕላም ቢን ባውራ ስሜቱን መከተል ሲጀምር መንፈሳዊ ደረጃውን አባከነ ወይም አጣ፡፡ ይህ ክስተት በሚከተለው አኳኋን በቁርአን ተገልጿል፡-

﴿ وَٱتۡلُ عَلَيۡهِمۡ نَبَأَ ٱلَّذِيٓ ءَاتَيۡنَٰهُ ءَايَٰتِنَا فَٱنسَلَخَ مِنۡهَا فَأَتۡبَعَهُ ٱلشَّيۡطَٰنُ فَكَانَ مِنَ
ٱلۡغَاوِينَ ١٧٥ وَلَوۡ شِئۡنَا لَرَفَعۡنَٰهُ بِهَا وَلَٰكِنَّهُۥٓ أَخۡلَدَ إِلَى ٱلۡأَرۡضِ وَٱتَّبَعَ هَوَىٰهُۚ فَمَثَلُهُۥ
كَمَثَلِ ٱلۡكَلۡبِ إِن تَحۡمِلۡ عَلَيۡهِ يَلۡهَثۡ أَوۡ تَتۡرُكۡهُ يَلۡهَثۚ ذَّٰلِكَ مَثَلُ ٱلۡقَوۡمِ
ٱلَّذِينَ كَذَّبُواْ بِـَٔايَٰتِنَاۚ فَٱقۡصُصِ ٱلۡقَصَصَ لَعَلَّهُمۡ يَتَفَكَّرُونَ ١٧٦ ﴾ الأعراف: ١٧٥ - ١٧٦

‹‹የዚያንም ተአምራታችንን የሰጠነውንና ከእርሱ የወጣውን፣ ሰይጣንም ያስከተለውን፣ ከጠማሞቹ የሆነውን ሰው ወሬ በእነርሱ ላይ አንብብላቸው፡፡ በሻንም ኖሮ በርሷ ከፍ ባደረግነው ነበር፡፡ እርሱ ግን ወደ ምድር ተዘነበለ፡፡ ፍላጎቱንም ተከተለ፡፡ ብጤውም ብታባርረው ምላሱን አውጥቶ እንደሚያለከልክ ወይም ብትተወው ምላሱን አውጥቶ

የሚያለከልክ እንደሆነ ውሻ ነው፡፡ ይህ የእነዚያ በአንቀጾቻችን ያስተባበሉት ሕዝቦች ምሳሌ ነው፡፡ …›› (አል-አእራፍ ፡ 175-176)

ሌላው በእምነት ልቡ አጊጦና ባለው ነገር ተብቃቅቶ ሲኖር የነበረና ከዚያ በኋላ ግን በዓለማዊ መጠቃቀሚያ ክፉኛ የተታለለውና ቀናውን መንገድ የሳተው ሰእለባ ነው፡፡ ሰእለባ ዘላለማዊቷንና የማትጠፋ የሆነችውን ሃገር በቅርቢቱና ፈጣን በሆነችው ብልጭልጭ ሃገር (ዱንያ) የቀየረ ከንቱ ሰው ነው፡፡ አብዛኛውን ጊዜውን በመስጊድ ውስጥ ከነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) ጋር በመቀመጥ ንግግራቸውን ያዳምጥ ነበር፡፡ በኋላ ላይ ግን ለገንዘብና ለኃብት ባደረበት ታላቅ ጉጉት የተነሣ ያንኑ መንገድ ተከትሎ በመሄድ የብዙ ሲሳይ ባለቤት ሆነ፡፡ ከዚያ በኋላ ከሙስሊሙ ማህበረሰብ ተነጥሎ በመሄድ ከመጪው ዓለም ዝግጅት ራሱን አቀበ፡፡

ይህ በእንዲህ እያለም ከነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) የተላኩና የዘካን ገንዘብ የሚሰበስቡ ልኡካን ወደርሱ ተልከው ዘካ እንዲከፍል ሲጠይቁት አሻፈረኝ አለ፡፡ በዚህ መጥፎ አድራጐቱም ከመናፍቃን ጐራ ራሱን አስገባ፡፡ መጨረሻውንም አበላሸ፡፡ ኋላ ላይ ተጸጽቶ የነቢዩን (ሰ.ዐ.ወ.) ንግግርም በማስታወስ ወደ መልካም ሥራ ለመመለስ ቢያስብም ጊዜው ረፍዶበት ነበር፡፡ የአላህን መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) ይቅርታ ለማግኘት ብዙ ሙከራዎችን ማድረጉ አልቀረም፡፡ በመጨረሻ ከእርሱ ጋር ሲለያዩ የተናገሩት ንግግር እንደ ገደል ማሚቶ በጆሮው ላይ ያቃጭልበት ነበር፡፡

‹‹ሳእለባ ሆይ! ብዙ ሃብት አከማችተህ ከማትብቃቃና አላህንም የማታመሰግን ከምትሆን ይልቅ በጥቂት ነገር ብትብቃቃና አመስጋኝ ብትሆን ይበልጥልሃል፡፡›› (የጦበሪና ኢብን ከሲር ተፍሲርን ይመልከቱ)፡፡

በኢስላማዊ ሕግ ታላቅ እውቀት እንደነበረው የሚታወቀው ሱፍያን አስ-ሰውሪ ከእድሜው የበለጠ ያረጀ መስሎ ይታይ ነበር፡፡ ይህ ሊሆን የቻለው ለምን እንደሆነ ለሚጠይቁት ሰዎችም እንዲህ በማለት ይመልስላቸው ነበር፡- ‹‹አንድ መምህር (ሼኽ) ነበረኝ፡፡ ይህ ሰው ብዙ ትምህርቶችን አስተምሮኛል፡፡ ሆኖም ግን የመጨረሻውን እስትንፋሱን ሲያወጣ (ሲሞት) ሸሃዳን (ከሊመቱ ተውሂድን) ከአንደበቱ ሊያወጣ

ፈጽሞ አልቻለም፡፡ ሸሃዳ እንዲያደርግ ብዙ ጥረት ባደርግም እርሱ ግን አልሆነለትም፡፡ ይህን ካየሁ በኋላ በሁኔታው በመደንገጤ ሃሳብና ትካዜ አስረጀኝ፡፡

እንግዲህ ሞት ወደኛ ሲመጣና መጨረሻችን ሲያምር ነው የምንረጋጋው፡፡ የፈርዖን አስማተኞች እንዳጋጠማቸው ብጤ የሕይወት ዘመናቸውን ሁሉ አላህን ሲያምጹ ኖረው መጨረሻቸው ያማረ ብዙ ናቸው፡፡ በሌላ በኩል ደግሞ ሕይወታቸውን ሙሉ አላህን ሲያመልኩና በቀናው ጎዳና ሲመላለሱ ኖረው ሊሞቱ አካባቢ የጥመትን መንገድ የሚይዙ አሉ፡፡ አላህ ይጠብቀንና ከእነዚህም መካከል ቃሩን፣ ባዕለምና ሰእለባ ይጠቀሳሉ፡፡ ስለሆነም አንድ ሰው የሚገኝበት መንፈሳዊ ደረጃ የቱንም ያህል ይሁን የነፍሱ ዝንባሌና ሰይጣን ሁልጊዜም እርሱን ለማዋረድ እየተጠባበቁት ይገኛሉ፡፡ ትክክለኛው ሰዓት ሲያጋጥማቸውም ከአላህ መንገድ ሊያስለቅቁት ይረባረባሉ፡፡ ሰይጣን በቁርዓን እንደተጠቀሰው በእርሱ (አደምን ማለቱ ነው) ምክንያት እንደተባረረ ብቀላ የሚያካሂድ መሆኑን ሲገልጽ እንዲህ ብሏል፡-

﴿ قَالَ فَبِمَآ أَغۡوَيۡتَنِي لَأَقۡعُدَنَّ لَهُمۡ صِرَٰطَكَ ٱلۡمُسۡتَقِيمَ ١٦ ثُمَّ لَأٓتِيَنَّهُم مِّنۢ بَيۡنِ أَيۡدِيهِمۡ وَمِنۡ خَلۡفِهِمۡ وَعَنۡ أَيۡمَٰنِهِمۡ وَعَن شَمَآئِلِهِمۡۖ وَلَا تَجِدُ أَكۡثَرَهُمۡ شَٰكِرِينَ ١٧ ﴾ الأعراف: ١٦ - ١٧

‹‹ስለ አጠመምከኝም ለእነርሱ በቀጥተኛው መንገድ ላይ በእርግጥ እቀመጥባቸዋለሁ፡፡ አለ፡፡ ከዚያም ከስተፊቶቻቸው፣ ከኋላቸውም፣ከቀኞቻቸውም፣ ከግራዎቻቸውም በእርግጥ እመጣባቸዋለሁ፡፡ አብዛኛዎቻቸውንም አመስጋኞች ሆነው አታገኛቸውም (አለ)፡፡›› (አል-አዕራፍ፡ 17)

ሰይጣን ይህን ካለ በኋላ አላህን አንድ ውለታ እንዲያደርግለት ጠየቀ፡፡ እርሱም የፍርዱ ቀን እስኪመጣና የሰው ልጆች ከየመቃብሮቻቸው ወጥተው ለፍርድ ከዓለማቱ ጌታ ፊት እስኪቆሙ ድረስ አላህ እንዲያቆየው ነው፡፡ አላህም ይህን ጥያቄውን ተቀበለው፡፡ ከዚያም

ሰይጣን እውነተኛ  አማኞች ካልሆኑ በስተቀር ከእርሱ ወጥመድ ማንም እንደማያመልጥ እንዲህ በማለት ማሃላውን እየደረደረ ተናገረ፡-

﴿ قَالَ فَبِعِزَّتِكَ لَأُغْوِيَنَّهُمْ أَجْمَعِينَ ﴿٨٢﴾ إِلَّا عِبَادَكَ مِنْهُمُ ٱلْمُخْلَصِينَ ﴿٨٣﴾ ﴾ ص: ٨٢ - ٨٣

‹‹(እርሱም) አለ፤ በአሸናፊነትህ ይሁንብኝ በመላ አሳስታቸዋለሁ፡፡ ከእነርሱ ምርጥ የሆኑት ባሮችህ ብቻ ሲቀሩ፡፡›› (ሷድ ፡ 82-83)

ስለዚህም ከሰው ልጅ ውስጥ ነቢይ ካልሆነ በስተቀር ከዚህ አደገኛ ዛቻ የሚያመልጥ የለም ማለት ነው፡፡ ለዚህም ነው ሁሉም አማኞች አላህ የሰጣቸውን ፀጋ በማመስገን፣ ትዕዛዙን በመፈጸምና ክልከላዎቹንም በመከልከል ቀጥ ማለት ያለባቸው፡፡ ከሞት አስፈሪ ትዕይንትና በዚያ ጊዜ ከሚመጣው አደጋ መዳኛው ብቸኛ መንገድ ሕይወትን አላህን በመፍራት ማሳለፍ ነው፡፡ ሞት የማይቀር የሰው ልጅ እዳ መሆኑን አውቀው ሲሰናዱ ለኖሩ ሰዎች አስፈሪ ሳይሆን ከጌታቸው ጋር የሚገናኙበትን ጊዜ የሚያቀርብላቸው በመሆኑ ወደው ይቀበሉታል፡፡

የአላህ መልእክተኛ (ሰ.0.ወ.) ይህን ዓለም ተሰናብተው ወደ መጪው ዓለም በሞት  የተሸጋገሩበት የመጨረሻ ሰዓት በጣም አስደናቂ ናት፡፡ እርሳቸው በእርግጥም ሕይወታቸውን ሁሉ የአላህን ትዕዛዝ በመጠበቅና እርሱን ከልባቸው በማምለክ ያሳለፉ በመሆኑ የመጨረሻዎቹ ሰዓታቶቻቸው የሙሽርነት ምሽት የሚመስሉና ያማሩ ነበሩ፡፡ ዓኢሻና ዓሊ (ረ.0.) እንዳስተላለፉት ‹‹የአላህ ነቢይ  በዚህች ዓለም ላይ ለመጨረሻ ጊዜ ባሳለፏቸው ሶስት ቀናት አላህ መልአኩ ጂብሪልን እየላከ ስለጤንነታቸው እንዲጠይቃቸው ያደርግ ነበር፡፡ በመጨረሻው ቀን ግን ጅብሪል የሞት መልአክ የሆነውን አዝራኢልን አስከትሎ ነበር የመጣው፡፡ ከዚያም እንዲህ አለ፡-

‹‹የአላህ  ነቢይ ሆይ! የሞት መልአክ ለመግባት ፈቃድ እየጠየቀ ነው፡፡ እስከአሁን ድረስ ከአደም ልጅ የማንንም ፈቃድ ጠይቆ አያውቅም፡

፡ ከአንተ በኋላም ከማንም ፈቃድ አይጠይቅም፡፡ እባክህ እንዲገባ ፍቀድለት!››

ከዚያም የሞት መልአክ ወደ እርሳቸው ገብቶ ከፊት ለፊታቸው ከቆመ በኋላ እንዲህ አለ፡- ‹‹የአላህ መልእክተኛ ሆይ! ኃያሉ አላህ ወደ አንተ እንድመጣና ማንኛውንም ትዕዛዝህን እንድቀበል ልኮኛል፡፡ ከፈለግህ ነፍስህን ልውሰዳት፡፡ ካልፈለግክ ደግሞ ትቸልህ እሄዳለሁ፡፡›› የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) በዚህ ጊዜ እንዲህ በማለት ጠየቁት፡- ‹‹የሞት መልአክ ሆይ! በእውነቱ ይህንን ታደርጋለህ?›› አዝራኢልም ‹‹እኔ ሁሉንም ያንተን ትዕዛዝ እንዳከብር ነው የተላክሁት›› አለ፡፡ ጂብሪል (ዐ.ሰ.) በዚህ ጊዜ እንዲህ አለ፡- ‹‹አህመድ ሆይ! ኃያሉ አላህ አንተን ለማግኘት ናፍቋል!›› ነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ) እንዲህ አሉ፡- ‹‹ከአላህ ዘንድ ያለው ይበልጥ የተሻለና ዘላቂም ነው፡፡ የሞት መልአክ ሆይ! የታዘዝከውን ፈጽም፡፡ ነፍሴን ውሰዳት፡፡››

ከዚያ በኋላ ነቢዩ ሙሐመድ (ሰ.ዐ.ወ) ከጎናቸው በዕቃ ላይ ከተቀመጠ ውሃ እጃቸውን እያነከሩ ፊታቸውን ታጠቡበት፡፡ ከዚያም ‹‹ላኢላሃ ኢለላህ›› የሚለውን ቃል (ከሊማ) ከተናገሩ በኋላ ‹‹በእርግጥ ሞት ጣእር አለው!›› አሉ፡፡ ከዚያም እጆቻቸውን ወደ ላይ አድርገው ጣሪያውን እያዩ እንዲህ አሉ፡- ‹‹አላህ ሆይ! ረፊቂል አዕላ፣ ረፊቁልአዕላ (ከላይኛዎቹና አላህ ፀጋውን ከለገሣቸው አድርገኝ፣ ከላይኛዎቹ ጋር አድርገኝ)››

ይህን በመሰለ ሁኔታ ያ የሰው ልጆች ሁሉ ፈርጥ፣ ክቡር ፍጡር፣ ለነፍሳቸው ያደሩ፣ ከዚህኛው አላፊ ሕይወት ወደ መጪውና ዘላለማዊው ሕይወት ተሸጋገሩ፡፡

የሞትን አስፈሪ ገጽታ ለመጋፈጥና ይህን የመሰለ ዕድል ለማግኘት ማንኛውም ሰው ራሱን መቆጣጠርና የነፍሱን ዝንባሌ መግታት መቻል አለበት፡፡ እንዲሁም ሕይወቱን በመለኮታዊው ሕግ ሥር አውሎ መምራትና በዚህ ዓይነት ሁኔታ የመጨረሻውን እስትንፋሱን ማውጣት ይኖርበታል፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَٱعۡبُدۡ رَبَّكَ حَتَّىٰ يَأۡتِيَكَ ٱلۡيَقِينُ ٩٩ ﴾ الحجر: ٩٩

‹‹እውነቱም (ሞት) እስኪመጣህ ድረስ ጌታህን ተገዛ፡፡›› (አል-ሒጅር፡99)

ይህ የቁርዓን አንቀጽ የያዘው መልእክት ታላቅና ሁሉንም የአላህ ባሮች የሚገዛ ነው፡፡ ማንም ብልህና አስተዋይ ሕሊናን የተቸረ ሰው አላፊ በሆነችውና እርባና በሌላት የዚህች ዓለም ሕይወት መታለል የለበትም፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَءَاثَرَ ٱلۡحَيَوٰةَ ٱلدُّنۡيَا ٣٨ فَإِنَّ ٱلۡجَحِيمَ هِيَ ٱلۡمَأۡوَىٰ ٣٩ وَأَمَّا مَنۡ خَافَ مَقَامَ رَبِّهِۦ وَنَهَى ٱلنَّفۡسَ عَنِ ٱلۡهَوَىٰ ٤٠ فَإِنَّ ٱلۡجَنَّةَ هِيَ ٱلۡمَأۡوَىٰ ٤١ ﴾ النازعات: ٣٨ - ٤١

‹‹ቅርቢቱንም ሕይወት የመረጠ ገሃነም እርሱ በእርግጥ መኖሪያው ናት፡፡ በሱ ፊት መቆምን የፈራ ሰውማ ነፍሱንም ከዝንባሌዋ የከለከለ ገነት እርሷ በእርግጥ መኖሪያው ናት፡፡›› (አን-ናዚአት፡ 38-41)

አላህ በተጨማሪም እንዲህ ይላል፡-

﴿ إِنَّ ٱلَّذِينَ لَا يَرۡجُونَ لِقَآءَنَا وَرَضُواْ بِٱلۡحَيَوٰةِ ٱلدُّنۡيَا وَٱطۡمَأَنُّواْ بِهَا وَٱلَّذِينَ هُمۡ عَنۡ ءَايَٰتِنَا غَٰفِلُونَ ٧ أُوْلَٰٓئِكَ مَأۡوَىٰهُمُ ٱلنَّارُ بِمَا كَانُواْ يَكۡسِبُونَ ٨ ﴾

‹‹እነዚያ መገናኘታችንን የማይፈሩ፣ ቅርቢቱንም ሕይወት የወደዱ፣ በእርሷም የረኩ፣ እነዚያም እነርሱ ከአንቀፆቻችን ዘንጊዎች የሆኑ፣ እነዚያ ይሰሩት በነበሩት ምክንያት መኖሪያቸው በእሳት ውስጥ ነው፡፡›› (ዩኑስ፡ 7-8)

አላህን የማስታወስን ፀጋ ለማግኘት የሚሻ ሰው ልቡን ከሽርክ (ማጋራትና) ቆሻሻ ነገሮች ማጽዳት አለበት፡፡ ያን ጊዜ በልቡ ላይ የእውነትና በሃቅ የመስራት ፀሐይ ፍንትው ብላ ትወጣለች፡፡ በሌላ በኩል ደግሞ አላህን ማስታወስን የተወ ሰው መንፈሳዊ ድቅቀት ያገኘዋል፡፡

ሞራሉ ይላሽቃል፡፡ ሕሊናውም ይደንዛል፡፡ እንደ እንስሳት ወይም ከዚያ በታች የተዋረደ ይሆናል፡-

﴿ وَلَا تَكُونُوا۟ كَٱلَّذِينَ نَسُوا۟ ٱللَّهَ فَأَنسَىٰهُمْ أَنفُسَهُمْ ۚ أُو۟لَـٰٓئِكَ هُمُ ٱلْفَـٰسِقُونَ ﴿١٩﴾ ﴾ الحشر: ١٩

‹‹እንደ እነዚያም አላህን እንደረሱትና ነፍሶቻቸውን እንዳስረሳቸው (ሰዎች) አትሁኑ፡፡ እነዚያ እነርሱ አመጸኞቹ ናቸው፡፡›› (አል-ሐሽር፡19)

በእርግጥም አላህን በማስታወስ ያልታነጸ መንፈስና ልብ የሰይጣን መጫወቻ መሆኑ አይቀሬ ነው፡፡ ሁልጊዜም ቢሆን አላህን ማስታወስና ሞትን መፍራት ልብን (ቀልብን) ሕያው ያደርጋል፡፡ ይህ እንዳይሆን የሚፈልገውና የሰው ልጆች ሁሉ ጠላት ኢብሊስ (ሰይጣን) ሁልጊዜም እኛን ለማጨናነቅና አላህን የምናስታውስበት ጊዜ እንዳናገኝ ለማድረግ ይረባረባል፡፡ ስለሆነም በተለያዩ ጉዳዮች መንፈሳችን እንዲያዝ ያደርጋል፡፡ አላህ ይህን ሁሉ ነገር ስለሚያውቅ ከሰይጣን ተንኮል እንድንጠበቅ እንዲህ የሚሉ የቁርአን አንቀፆችን አውርዷል፡-

﴿ أَلَمْ أَعْهَدْ إِلَيْكُمْ يَـٰبَنِىٓ ءَادَمَ أَن لَّا تَعْبُدُوا۟ ٱلشَّيْطَـٰنَ ۖ إِنَّهُۥ لَكُمْ عَدُوٌّ مُّبِينٌ ﴿٦٠﴾ وَأَنِ ٱعْبُدُونِى ۚ هَـٰذَا صِرَٰطٌ مُّسْتَقِيمٌ ﴿٦١﴾ وَلَقَدْ أَضَلَّ مِنكُمْ جِبِلًّا كَثِيرًا ۖ أَفَلَمْ تَكُونُوا۟ تَعْقِلُونَ ﴿٦٢﴾ ﴾ يس: ٦٠ - ٦٢

‹‹የአደም ልጆች ሆይ! ሰይጣንን አትገዙ፤ እርሱ ለእናንተ ግልጽ ጠላት ነውና በማለት ወደእናንተ አላዘዝኩምን? ተገዙኝም፤ ይህ ቀጥተኛ መንገድ ነው (በማለትም)፡፡ ከእናንተም ብዙን ፍጡር በእርግጥ አሳስቷል የምታውቁም አልነበራችሁምን?›› (ያሲን ፡ 60-62)

ኃያሉ አላህ በብዙ የቁርዓን አንቀፆች በግልጽ የሚያስጠቀቅቀን ድርጊቶቻችን፣ ፍላጎቶቻችንና አጠቃላይ ፀባያችንን እንድንቆጣጠርና

እንድናርም ነው፡፡ ይህን የማናደርግ ከሆነ ሕይወታችን በሀዘን ማሳረጓ የማይቀር ነው፡፡ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ ٱتَّقُواْ ٱللَّهَ حَقَّ تُقَاتِهِۦ وَلَا تَمُوتُنَّ إِلَّا وَأَنتُم مُّسۡلِمُونَ ١٠٢﴾

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! አላህን ተገቢውን መጠንቀቅን ተጠንቀቁት፤ እናንተም ሙስሊሞች ሆናችሁ እንጅ አትሙቱ፡፡ ›› (አሊ-ኢምራን ፡ 102)

እዚህ ላይ አጽንኦት ሊያገኝ የሚገባው ሃሳብ ሁላችንም ቁርዓን ባበጀልን የሕይወት ዘይቤ እንመራ የሚል ነው፡፡ ይህች ዓለም አታላይ ነች፡፡ ሰው ነፋስን እንደመከተል በሚቆጠር ሩጫ ሲባዝንና ከኋላ ከኋላዋ ሲሮጥ ፈጽሞ ሊጨብጣት አልቻለም፡፡ በመጨረሻ በሞት መዳፎች ሲጨመደድና በፍርዱ ቀን ከአላህ ፊት መቅረቡን ሲገነዘብ ነው የሚባንነው፡፡

﴿كَأَنَّهُمۡ يَوۡمَ يَرَوۡنَهَا لَمۡ يَلۡبَثُوٓاْ إِلَّا عَشِيَّةً أَوۡ ضُحَىٰهَا ٤٦﴾ النازعات: ٤٦

‹‹እነርሱ በሚያዩዋት ቀን ምሽቷን ወይም ረፋዷን እንጅ ያልቆዩ ይመስላሉ፡፡››(አን-ናዚአት፡ 46)

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلنَّاسُ ٱتَّقُواْ رَبَّكُمۡۚ إِنَّ زَلۡزَلَةَ ٱلسَّاعَةِ شَيۡءٌ عَظِيمٞ ١ يَوۡمَ تَرَوۡنَهَا تَذۡهَلُ كُلُّ مُرۡضِعَةٍ عَمَّآ أَرۡضَعَتۡ وَتَضَعُ كُلُّ ذَاتِ حَمۡلٍ حَمۡلَهَا وَتَرَى ٱلنَّاسَ سُكَٰرَىٰ وَمَا هُم بِسُكَٰرَىٰ وَلَٰكِنَّ عَذَابَ ٱللَّهِ شَدِيدٞ ٢﴾ الحج: ١ - ٢

‹‹እናንተ ሰዎች ሆይ! ጌታችሁን ፍሩ የሰዓቲቱ እንቅጥቃጤ በጣም ከባድ ነገር ነውና፡፡ በምታዩዋት ቀን አጥቢ ሁሉ ከአጠባችው ልጅ ትፈዛለች፡፡ የእርግዝና ባለቤት የሆነችም ሁሉ እርጉዟን ትጨነግፋለች፡፡ ሰዎቹንም (በድንጋጤ ብርታት) የሰከሩ ሆነው ታያለህ፡፡ እነርሱም (ከመጠጥ) የሰከሩ አይደሉም፡፡ ግን የአላህ ቅጣት ብርቱ ከመሆኑ እንጂ›› (አል-ሐጅ ፡ 1-2)

## ምዕራፍ ሦስት

# የመጨረሻው እስትንፋስ በጭጋግ

# ያልተጋረደ መስታዎት

የሰው ፍጻሜ ልክ በጭጋግ እንዳልተጋረደ ወይም እንዳልወየበ መስታወት መልካም እድልንም (ሰዓዳ) ሆነ መጥፎ እድልን (ሸቃዋ) ቁልጭ አድርጎ የሚያሳይ ክስተት ነው፡፡ ምክንያቱም ሰው የመጨረሻው ውጤቱ የሚወሰነው ሰውየው ባሳለፈው የሕይወት ዘይቤ ላይ ነውና፡፡ ሰው የዘራውን እንጂ ሌላን ሊያጭድ ከቶ አይቻለውም፡፡

በቁርዓን እንደተገለጸው ፈርዖን እድሜውን የፈጀው አላህን በማመጹ ነበር፡፡ እናም የሕይወት መስመሩ ሙሉ በሙሉ ስህተት እንደነበር የተገነዘበው በቀይ ባህር ውስጥ የመጨረሻውን እስትንፋሱን ሲያወጣ ነበር፡፡ ያሳለፋቸው በአመፅና በእኩይ ድርጊት የተሞሉ የግዛት ዘመናቱ የሃዘኑና የሰቆቃው ምንጭ ሊሆኑት ካልሆነ ምን ሊበጁት! እናም ሁሉም ነገር ከቁጥጥሩ ውጭ ሆነበር፡፡ መቸውም ሰው ነውና መፀፀት ስለማይቀር በመጨረሻ ላይ የማይጠቅም ፀፀቱን እንዲህ በማለት ገለፀ፡-

﴿ وَجَٰوَزۡنَا بِبَنِيٓ إِسۡرَٰٓءِيلَ ٱلۡبَحۡرَ فَأَتۡبَعَهُمۡ فِرۡعَوۡنُ وَجُنُودُهُۥ بَغۡيٗا وَعَدۡوًاۖ حَتَّىٰٓ إِذَآ أَدۡرَكَهُ ٱلۡغَرَقُ قَالَ ءَامَنتُ أَنَّهُۥ لَآ إِلَٰهَ إِلَّا ٱلَّذِيٓ ءَامَنَتۡ بِهِۦ بَنُوٓاْ إِسۡرَٰٓءِيلَ وَأَنَا۠ مِنَ ٱلۡمُسۡلِمِينَ ٩٠ ﴾ يونس: ٩٠

‹‹የእስራኤልም ልጆች ባህሩን አሳለፍናቸው፡፡ ፈርዖንና ሰራዊቱም ወሰን ለማለፍና ለመበደል ተከተሏቸው፡፡ መስጠምም ባገኘው ጊዜ፡- ‹‹አመንኩ እነሆ ከዚያ የእስራኤል ልጆች በርሱ ካመኑበት በስተቀር ሌላ አምላክ የለም፤ እኔም ከታዛዦቹ ነኝ አለ፡፡›› (ዩኑስ ፡ 90)

ሆኖም ግን ይህ የፈርዖን አባባል ከንቱና ጥበብ የጎደለው ነበር፡፡ ‹‹ሳያዩ (በገይብ) የሚያምኑ ብፁአን ናቸው፡፡›› የሚል አባባል አለ፡፡ ፈርዖን ግን ብዙ ተግሳጽ ተሰጥቶት፣ ብዙ ተለምኖና ተመክሮ አሻፈረኝ በማለት የኖረ ሰው ነው፡፡ በመጨረሻ ላይ የቀይ ባህር ውሃ በአፍና በአፍንጫው ሲገባበት ነበር በቁርጥ መያዙን የተገነዘበው፡፡ እናም ከላይ በቀረበው መልክ የሞት ሞቱን ዘላበደ፡፡ ሆኖም ግን ኃያሉ አላህ እንደሚከተለው በማለት ነበር አሁን መወራጨቱ እንደማያዋጣው የገነጸለት፡-

﴿ ءَآلۡـَٰٔنَ وَقَدۡ عَصَيۡتَ قَبۡلُ وَكُنتَ مِنَ ٱلۡمُفۡسِدِينَ ٩١ فَٱلۡيَوۡمَ نُنَجِّيكَ بِبَدَنِكَ لِتَكُونَ لِمَنۡ خَلۡفَكَ ءَايَةٗۚ وَإِنَّ كَثِيرٗا مِّنَ ٱلنَّاسِ عَنۡ ءَايَٰتِنَا لَغَٰفِلُونَ ٩٢ ﴾ يونس: ٩١ - ٩٢

‹‹ከአሁን በፊት በእርግጥ ያመጽክ፣ ከአጥፊዎችም የነበርክ ስትሆን አሁን? (ተባለ)፡፡ ዛሬማ ከኋላህ ላሉት ተዓምር ትሆን ዘንድ በድን ሆነህ (ከባህሩ) እናወጣሃለን (ተባለ)፡፡ …›› (ዩኑስ ፡ 91-92)

ስለሆነም በስሜታዊ ዝንባሌ ዥዋዥዌ ሲጫወቱ እድሜን ከጨረሱ በኋላ የሕይወት ጀንበር አቆልቁላ ልትጠልቅ ስትል አማኝ ነኝ ብሎ መወራጨት ዋጋ የሌለው ነገር ነው፡፡ በዓለማዊ መጠቃቀሚያና በስሜት ባህር የተዘፈቁ ሰዎች አንድ እለት አላህ መጥፎ አያያዝ የያዛቸው ጊዜ ወዮላቸው፡፡ ያኔ የመጪው ዓለም መጋረጃ ሁሉ

ይገላለጥና ሁሉንም ነገር በዓይነ ሥጋቸው ሲመለከቱ ምን ይውጣቸው ይሆን? ይህን አንኳር ሃቅ ኃያሉ አላህ በብዙ የቁርዓን አንቀፆች የገለጸው ሲሆን ቀጣዮቹ አንቀፆችም የሚያብራሩት ይህንኑ ነው፡-

﴿ كُلُّ نَفْسٍ ذَآئِقَةُ ٱلْمَوْتِ ۗ وَنَبْلُوكُم بِٱلشَّرِّ وَٱلْخَيْرِ فِتْنَةً ۖ وَإِلَيْنَا تُرْجَعُونَ ﴿٣٥﴾ ﴾ الأنبياء: ٣٥

‹‹ነፍስ ሁሉ ሞትን ቀማሽ ናት፤ ለመፈተንም በክፉም በበጎም እንሞክራችኋለን፡፡ ወደኛም ትመለሳላችሁ፡፡›› (አል-አንቢያ፡ 35)

﴿ ٱلَّذِى خَلَقَ ٱلْمَوْتَ وَٱلْحَيَوٰةَ لِيَبْلُوَكُمْ أَيُّكُمْ أَحْسَنُ عَمَلًا ۚ وَهُوَ ٱلْعَزِيزُ ٱلْغَفُورُ ﴿٢﴾ ﴾ الملك: ٢

‹‹ያ የትኛችሁ ሥራው ይበልጥ ያማረ መሆኑን ሊሞክራችሁ ሞትንና ሕይወትን የፈጠረ ነው፡፡ እርሱም አሸናፊው መሐሪው ነው፡፡ ›› (አል-ሙልክ ፡ 2)

ኢማም አል-ገዛሊ እንዲህ ይላሉ፡-

‹‹በዚህ ዓለም ላይ እውቀትን (ኢልምን) በመማር የሚገኘውን ደስታ ያላጣጣመ ሰው የመጪውን ዓለም ያማረ ሕይወት ማስተንተን አይችልም፡፡ አንድ ሰው በዚህች ዓለም ላይ ሰርቶ ያላሳለፋትን መልካም ነገር በመጪው ዓለም አያገኛትም፡፡ ማንም ቢሆን በዚህች ዓለም የተከለውን ፍሬ ነው በመጪው ዓለም የበሰለ ሆኖ የሚያገኘው፡፡ ሁሉም ሰው እንደ አኗኗሩ ይሞታል፡፡ እንደ አሟሟቱም ይቀሰቀሳል፡፡ በመጪው ዓለም ደስታ የምናገኘው አላህን በመፍራት በሰራነው መልካም ሥራ ልክ ነው፡፡››

ስለሆነም በእያንዳንዷ እስትንፋሳችን ራሳችንን አንድም ለታላቅ ቅጣት ወይም ማለቂያ ለሌለው ደስታና ሽልማት እያዘጋጀን ነው፡፡ ኃያሉ አላህ እንዲህ በማለት ይገስፀናል፡-

﴿ يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ قُوٓاْ أَنفُسَكُمۡ وَأَهۡلِيكُمۡ نَارٗا وَقُودُهَا ٱلنَّاسُ وَٱلۡحِجَارَةُ عَلَيۡهَا مَلَٰٓئِكَةٌ غِلَاظٞ شِدَادٞ لَّا يَعۡصُونَ ٱللَّهَ مَآ أَمَرَهُمۡ وَيَفۡعَلُونَ مَا يُؤۡمَرُونَ ٦ ﴾ التحريم: ٦

‹‹እናንተ ያመናችሁ ሆይ! ነፍሶቻችሁንና ቤተሰቦቻችሁን መቀጣጠያዋ ሰዎችና ድንጋዮች ከሆነች እሳት ጠብቁ፡፡ በእርሷ ላይ ጨካኞችና ኃይለኞች የሆኑ መላእክት አሉ፡፡ አላህን ያዘዛቸውን ነገር (በመጣስ) አያምጹም፡፡ የሚታዘዙትንም ሁሉ ይሰራሉ፡፡›› (አት-ተሕሪም፡ 6)

ኃያሉ አላህ በተጨማሪም እንዲህ ይላል፡-

﴿ وَإِذَا ٱلۡجَحِيمُ سُعِّرَتۡ ١٢ وَإِذَا ٱلۡجَنَّةُ أُزۡلِفَتۡ ١٣ عَلِمَتۡ نَفۡسٞ مَّآ أَحۡضَرَتۡ ١٤ ﴾ التكوير: ١٢ - ١٤

‹‹ገሀነምም በተነደደች ጊዜ፤ ገነትም በተቀረበች ጊዜ፤ ነፍስ ሁሉ (ከሥራ) ያቀረበችውን ታውቃለች፡፡›› (አት-ተክዊር፡ 12-14)

﴿ فَأَيۡنَ تَذۡهَبُونَ ٢٦ ﴾ التكوير: ٢٦

‹‹ታዲያ ወዴት ትሄዳላችሁ?›› (አት-ተክዊር፡ 26)

ትርፍና ኪሳራ፣ ማግኘትና ማጣት ያሉት በዚህች ዓለም ላይ ብቻ ነው፡፡ በመጪው ዓለም ግን ያለው ምርመራ ብቻ ነው፡፡ አማኝ ሰው መጨረሻው ያምር ዘንድ ነፍሱን ከአንጉል ዝንባሌዋ ማጽዳትና በመልካም ምግባርና በሰናይ ባሕሪ እንድታሸበርቅ ማድረግ ይኖርበታል፡፡ ይህም አላህን መፍራትን (ተቅዋን) ያላብሳል፡፡

ነፍስን ይበልጥ ለማጽዳትና ወደ ፈጣሪዋ ለማቃረብ አላህንና መልእክተኛውን (ሰ.ዐ.ወ.) መውደድ፣ እንዲሁም ይህንንም በመልካም መግለጽ ግድ ይላል፡፡ ኃያሉ አላህ እንዲህ ይላል፡-

﴿ قُلۡ إِن كَانَ ءَابَآؤُكُمۡ وَأَبۡنَآؤُكُمۡ وَإِخۡوَٰنُكُمۡ وَأَزۡوَٰجُكُمۡ وَعَشِيرَتُكُمۡ وَأَمۡوَٰلٌ ٱقۡتَرَفۡتُمُوهَا وَتِجَٰرَةٞ تَخۡشَوۡنَ كَسَادَهَا وَمَسَٰكِنُ تَرۡضَوۡنَهَآ أَحَبَّ إِلَيۡكُم مِّنَ ٱللَّهِ وَرَسُولِهِۦ وَجِهَادٖ فِي سَبِيلِهِۦ فَتَرَبَّصُواْ حَتَّىٰ يَأۡتِيَ ٱللَّهُ بِأَمۡرِهِۦۗ وَٱللَّهُ لَا يَهۡدِي ٱلۡقَوۡمَ ٱلۡفَٰسِقِينَ ٢٤ ﴾ التوبة: ٢٤

‹‹አባቶቻችሁና ወንዶች ልጆቻችሁ፣ ወንድሞቻችሁም፣ የሰበሰባችኋቸው ሃብቶችም፣ መክሰሯን የምትፈሯት ንግድም፣ የምትወዷቸው መኖሪያዎችም ከእናንተ ዘንድ ከአላህና ከመልእክተኛው በርሱ መንገድም ከመታገል ይበልጥ የተወደዱ እንደሆኑ አላህ ትእዛዙን እስኪያመጣ ድረስ ተጠባበቁ በላቸው፡፡ አላህም አመጸኞች ሕዝቦችን አይመራም፡፡ ›› (አት-ተውባህ፡ 24)

ነፍስን በማጽዳት ወደ አላህ ለመቃረብና ይበልጥ እርሱን ለማስደሰት የመልካም ሥራ ቁንጮ የሆነውን የአላህን ሕግጋት መጠበቅን የሚያክል ነገር የለም፡፡

አብደላህ ኢብን አባስ (ረ.ዐ.) እንዲህ ብለዋል፡-

‹‹አንድ ቀን ከነቢዩ (ሰ.ዐ.ወ.) ኋላ ነበርኩ፡፡ እንዲህም አሉኝ፡-

‹‹አንተ ልጅ፤ እኔ ጥቂት ቃላቶችን ላስተምርህ፡፡ የአላህን ትእዛዝ ጠብቅ፡፡ እርሱም ይጠብቅሃልና፡፡ አላህን ጠብቀው በፊት ለፊት ታገኘዋለህና፡፡ ስትጠይቅ አላህን ጠይቅ፤ እርዳታ ከፈለግህ በአላህ ተረዳ፡፡ ሕዝቦች ሁሉ ሊጠቅሙህ ቢሰበሰቡ አይጠቅሙህም፤ አላህ በእርግጥ የወሰነልህ ነገር ሲቀር፡፡ ሊጎዱህ ቢሰበሰቡ ሊጎዱህ አይችሉም፡፡ አላህ በእርግጥ በአንተ ላይ የወሰነብህ ነገር ቢሆን እንጂ፡፡ ብእሮች ተነስተዋል፤ ገጾቹም ደርቀዋል፡፡›› (ቲርሚዚ ዘግበውታል)

በጎ ምግባራት፣ ጥሩ ፀባይ፣ የሰው ልጆችን ማገልገል እነዚህና ሌሎችም ወደ አላህ የመቃረቢያ መንገዶች ናቸው፡፡ ኃያሉ አላህም መልካም ምግባር ማለት ፊትንና ግንባርን ብቻ መሬት ላይ መድፋት አለመሆኑን በሚከተለው የቁርዓን አንቀጽ ይገልጻል፡፡

﴿ لَّيْسَ ٱلْبِرَّ أَن تُوَلُّوا۟ وُجُوهَكُمْ قِبَلَ ٱلْمَشْرِقِ وَٱلْمَغْرِبِ وَلَـٰكِنَّ ٱلْبِرَّ مَنْ ءَامَنَ بِٱللَّهِ وَٱلْيَوْمِ ٱلْـَٔاخِرِ وَٱلْمَلَـٰٓئِكَةِ وَٱلْكِتَـٰبِ وَٱلنَّبِيِّـۧنَ وَءَاتَى ٱلْمَالَ عَلَىٰ حُبِّهِۦ ذَوِى ٱلْقُرْبَىٰ وَٱلْيَتَـٰمَىٰ وَٱلْمَسَـٰكِينَ وَٱبْنَ ٱلسَّبِيلِ وَٱلسَّآئِلِينَ وَفِى ٱلرِّقَابِ وَأَقَامَ ٱلصَّلَوٰةَ وَءَاتَى ٱلزَّكَوٰةَ وَٱلْمُوفُونَ بِعَهْدِهِمْ إِذَا عَـٰهَدُوا۟ ۖ وَٱلصَّـٰبِرِينَ فِى ٱلْبَأْسَآءِ وَٱلضَّرَّآءِ وَحِينَ ٱلْبَأْسِ ۗ أُو۟لَـٰٓئِكَ ٱلَّذِينَ صَدَقُوا۟ ۖ وَأُو۟لَـٰٓئِكَ هُمُ ٱلْمُتَّقُونَ ﴿١٧٧﴾ ﴾ البقرة: ١٧٧

‹‹መልካም ሥራ ፊቶቻችሁን ወደ ምሥራቅና ምዕራብ አቅጣጫ ማዞር አይደለም፡፡ ግን መልካም ሥራ በአላህና በመጨረሻው ቀን፣ በመላእክትም፣ በመጻሕፍትም፣ በነቢያትም ያመነ ሰው ገንዘብንም ከመውደዱ ጋር ለዝምድና ባለቤቶችና ለየቲሞች፣ ለምስኪኖችም፣ ለመንገደኞችም፣ ለለማኞችም፣ ለባሪያዎችም (ነጻ መሆን) የሰጠ ሰውና ሶላቱንም ደንቡን ጠብቆ የሰገደ፣ ዘካንም የሰጠ ፣ ቃል ኪዳንም በገቡ ጊዜ ቃል ኪዳናቸውን የሞሉ (ሰዎች ሥራ) ነው፡፡ በችግር፣ በበሽታና በጦር ጊዜም ታጋሾችን (እናወድሳለን)፡፡ እነዚያም እውነትን የያዙ ናቸው፡፡›› (አል-በቀራህ፡ 177)

የሰማያትና የምድር፣ እንዲሁም በመካከላቸውም ያሉ ፍጡራን ሁሉ ጌታ የሆነውን አላህ ይበልጥ ለመቅረብ መልካም ሥራዎችን ማብዛት ያስፈልጋል፡፡ የአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) የመልካም ሥራ ቅርንጫፎች ብዙ መሆናቸውን በተከታዩ ሐዲስ ይገልጻሉ፡፡ ይህ መልካም ሥራም እንደ ሰደቃ (ምፅዋት) ይቆጠራል፡፡

ከአቡ ሁረይራ (ረ.ዐ) በተላለፈው ሐዲስ እንዲህ ብለዋል፡-

‹‹በእያንዳንዱ የሰው አካልና መገጣጠሚያ ላይ በየቀኑ (ለደህንነቱ ተግባራዊ ምሥጋና) ምጽዋት (ሶደቃ) አለበት፡፡ በሁለት

ሰዎች መካከል ፍትሕ ማስፈን ሶደቃ ነው፡፡ አንድ ሰው ከሚጓዝበት እንስሳ ጀርባ ላይ ሲወጣ ማገዝና መርዳት ወይም ከወጣ በኋላ እቃውን ማቀበል ሶደቃ ነው፡፡ መልካም ንግግርም ሶደቃ ነው፡፡ ለሶላት ስትሄድ የምትራመደው እያንዳንዱ እርምጃም ሶደቃ ነው፡፡ ከመንገድ ላይ እንቅፋት ማንሳትም ሶደቃ ነው፡፡››

እነዚህ ሁሉ የመልካም ምግባር ቅርንጫፎች እንዳሉ ሆነው በዋነኝነት የአላህን ውዴታ ለማግኘት የሚቻለው ግዴታ (ዋጅብ) የሆኑ የአምልኮት (ኢባዳ) ክፍሎችን በመፈጸም ነው፡፡

ከእነዚህ ግዴታ ከተደረጉብን የአምልኮት (ኢባዳ) አይነቶች ዋነኛው ሶላት ነው፡፡ በእምነትና በክሃዲነት መካከል የሚገኝ ታላቅ የሆነ፤ ከፈጣሪያችን አላህ ጋር የመገናኛ መንገድ ነው፡፡ ስለሆነም ደንቡን ጠብቀንና አላህን ፈርተን በአትኩሮት ልንሰግድ ይገባናል፡፡ ለባሮቹ አዛኝና ሩህሩህ የሆነው አላህ ሶላትን ደንቡን ጠብቆና እርሱን እየፈሩ መስገድ በመጪው ዓለም ለስኬት ለመብቃት መድህን እንደሚሆን ሲያረጋግጥ እንዲህ ይላል፡-

﴿ قَدۡ أَفۡلَحَ ٱلۡمُؤۡمِنُونَ ١ ٱلَّذِينَ هُمۡ فِي صَلَاتِهِمۡ خَٰشِعُونَ ٢ ﴾ المؤمنون: ١ - ٢

‹‹ምዕመናን ፍላጎታቸውን ሁሉ አገኙ (ዳኑ)፡፡ እነዚያ እነርሱ በስግደታቸው ውስጥ (አላህን) ፈሪዎች፡፡›› (አል-ሙእሚኑን፡1-2)

በሌላ የቁርዓን አንቀጽ ደግሞ እንዲህ በማለት ይናገራል፡-

﴿ فَوَيۡلٞ لِّلۡمُصَلِّينَ ٤ ٱلَّذِينَ هُمۡ عَن صَلَاتِهِمۡ سَاهُونَ ٥ ﴾ الماعون: ٤ - ٥

‹‹ለሰጋጆች ወዮላቸው ለእነዚያ እነርሱ ከስግደታቸው ዘንጊዎች ለሆኑት (ሰጋጆች)፡፡›› (አል-ማዑን ፡4-5)

አንድ ሰው ከአላህ መልእክተኛ (ሰ.ዐ.ወ.) ዘንድ በመምጣት፡-

‹‹የአላህ መልእክተኛ ሆይ! አጭር የሆነና ልቤ ውስጥ የሚገባ ምክር ይለግሱኝ፡፡›› አላቸው፡፡ እርሳቸውም እንዲህ አሉት፡- ‹‹ሶላት

ስትሰግድ ይህን ዓለም ተሰናብተህ እንደምትሄድና የመጨረሻ ሶላትህ እንደሆነ በማሰብ ስገድ። በኋላ ይቅርታ እንድትጠይቅ የሚያደርግህን ምንም ነገር አትናገር። እንዲሁም በሌሎች እጅ የሚገኝን ነገር (ሃብት) ችላ በል (ትኩረት አትስጥ)።›› (ኢብን ማጃህ፣ አህመድ ኢብን ሃንበል)

ከሶላት በመቀጠል ያሉት ዘካ፣ ፆምና ሐጅም በንጹህ ልቦናና በሙሉ ቁርጠኝነት (ንያ) ከተፈጸሙ ወደ ኃያሉ ጌታ አላህ እጅግ የሚያቃርቡ ተግባራት ናቸው። አላህ እርሱን በሩቁ ከሚፈሩትና የመልካም ሥራ መዝገቦቻቸውን በቀኝ እጃቸው ከሚቀበሉት ያድርገን፣ አሚን።

**=ተፈጸመ=**